ቪ. አይ. ሌኒን

# ኢምፔሪያሊዝም

## ከፍተኛው የካፒታሊዝም የዕድገት ደረጃ



ትርጉም

በኩራገ

ቪ. አይ. ሌኒን

# ኢምፔሪያሊዝም

## ከፍተኛው የካፒታሊዝም የዕድገት ደረጃ

ትርጉም

በኩራዝ

ሚያዝያ ፲፱፻፸፭ ዓ. ም.

# ማ ውጫ ፤

# መ ቅ ድ ም

ይህ « ኢምፔሪያሊዝም ከፍተኛው የካፒታሊዝም የዕድገት ደረጃ » የተሠኘው መጽሐፍ የተደረሰው በታ ወቀው የሩሲያ አብዮተኛና በመጀመሪያ የማርክሲዝምን ጽንሰ ሀሣቦች በግብር በተረጐመው ሌኒን ነው ። ምንም እንኳን መጽሐፉን ለመድረስ በአያሌ የቡርዧ ደራስያን የተጻፉ ጽሑፎችን እንዲያነብ አስፈላጊ ሆኖ ቢያገኘውም ለካፒታሊዝም የመጨረሻ የዕድገት ደረጃ ትክክለኛውን ሣይንሣዊ ትንታኔ የሰጠው ፥ ዓይነተኛ ባሕርዮችም የነጻ ንግድ ልውውጥ በሞኖፖሊ መተካት ፥ ገንዘባዊ ወረት መንገሥ ወዘተ . መሆናቸውን ያሳወቀው እሱ ነው ። ስለ ዚህ ፥ ማናቸውም በአሁኑ ከፍተኛ የታሪክ ወቅት አብዮት የሚያካሂድ ሀገር ፥ ወደደም ጠላም ፥ ዋና ጠላቱ ኢምፔ ሪያሊዝም መሆኑን ጠንቅቆ መገንዘብና ፥ ብሎም እሱን እንዴት እንደሚዋጋው ታክቲኩንና ስትራቴጂውን መቀ የስ ይኖርበታል ።

ሀገራችን በአሁኑ ወቅት በምታካሂደውም አብዮት ቀን ደኛ ጠላቷ ኢምፔሪያሊዝም በመሆኑ ፥ እያንዳንዱ አብ ዮተኛ ስለዚህ የጭቁኖች ጠላት ምንነት በሚገባ አውቆ ከውስጥና ከውጪ የሚሠነዘርበትን ጥቃትና የአብዮት ቅልበሣ ሴራ መዋጋት ይኖርበታል ።

ይህንኑ በመረዳት ፥ በተጨማሪም ጭቁኑ ባለፈው የፊውዶ ቡርዧ ሥርአት የመማር ዕድሉ የተወሰነ ስለ ነበረ ፥ ይህን በእንግሊዝኛ የቀረበ መጽሐፍ ወደ አማ ርኛ መልሶ ማቅረቡ በትምህርቱ ደረጃ ማነስ ምክን ያት የደረሰውን ችግር በመጠኑም ቢሆን ለማቃለል መዋ ጮውን ያበረክት ይሆናል ብሎ በማሰብ ፥ መጽሐፉ ተተርጉሟል ።

አንባቢያን የተሳሳተ ሀሣብ ሠፍሮ የተገኘበትን አካባቢ እንዲጠቁሙንና የተሻለ ጥራት እንዲኖረው ለማድረግ እንዲተባበሩ አብዮታዊ ግዴታቸውም መሆኑን ለማሳወቅ እንወዳዳለን ።

የግርጌ ማስታወሻዎች ለጊዜው ከምዕራፍ አስር ቀጥሎ ባሉት ገጾች ቀርበዋል ።

« ለወሣኙ ፍልሚያ ወደፊት »

« እናሸንፋለን »

# ኢምፔሪያሊዝም ፤ ከፍተኛው የካፒታ ሊዝም የዕድገት ደረጃ

## ለሕዝብ የቀረበ ማጠቃለያ ፤ 1.

### መ ግ ቢ ያ

ይህ ለአንባቢው የቀረበው መጽሔት በ1916 በዙሪክ ከተማ የተጻፈ ነው ። እዚህ እንድሠራ በተገደድኩባቸው ሁኔታዎች የእንግሊዝኛና የፈረንሣይኛ ሥነ ጽሑፎች እጥረት በተለይም የሩሲያኛ ሥነ ጽሑፍ ከፍተኛ እጥረት አጋጥሞኛል ። ይሁንና ፣ ስለ ኢምፔሪያሊዝም በእንግሊዝኛ የተጻፈውን ከፍተኛ ጥናት የጂ. ኤ. ሆብስንን መጽሐፍ ፣ በኔ ሃሣብ ያስፈልገዋል ብዬ የገመትኩትን ጥንቃቄ በማድረግ ፣ በጥቅም ላይ አውዬዋለሁ ።

ይህ መጽሔት የዛሪስቱን ሣንሱር እንደሚያልፍ ተደርጎ የቀረበ ነው ። ስለሆነም ከንድፈ ሃሣቡ ውጪ ሣልወጣ በተለይም በኤኮኖሚያዊው ላይ በማትኮር ብቻ ሳይሆን ፖለቲካውም ላይ ጥቂት አስፈላጊ ትዝብቶችን በታላቅ ጥንቃቄ አቀነባብሬ ፣ በጥቆማ መልክ ፣ ለማለት የፈለግሁትን ሃሣብ በውስጠ ታዋቂ ቋንቋ በመሸፈን በዚያ በርኩስ የኤዞፕ ቋንቋ ፣ ዛሪዝም አብዮታውያን «ሕጋዊ» ጽሑፍ ለማቅረብ ብእራቸውን በሚያነሱበት ጊዜ እንዲጣጠኑት የሚያስገድዱበት ቋንቋ፣ በትክክል ለመግለጽ ነበር።

በአሁኑ እንዳሻኝ ለመሆን በምችልበት ጊዜ በመጽሔቱ ውስጥ ተጣመው ፤ ኩርትምትም ብለው ፣ በሣንሱሩ ምክንያት ታንቀው የቀረቡትን ሃሳቦች መልሶ ማንበብ ምንኛ ያቆስላል ። ኢምፔሪያሊዝም የሶሺሊስት አብ

ዮት ዋዜማ መሆኑ ፣ ሶሺያል ትምክህተኛነት (ሶሻሊዝም በቃላት ፣ ትምክህተኛነት በግብር) ሶሽያሊዝምን መክዳት ፣ ወደ ቡርዧው ወገን ከድቶ መግባት በመሆኑ ወዘተረፈ በነዚህ ሁኔታዎች ላይ « በጕስቋላ » (ስላቪሽ) ቋንቋ መናገር ነበረብኝ ፣ እና ውጪ ሀገር በነበርኩበት ጊዜ ከ1914—17 በመጽሔቱ ውስጥ በቅርብ ጊዜ አዲስ እትም የሚወጣላቸውን ያቀረብኳቸውን 8 ጽሑፎች እንዲያነብ ፍላጐት ያለውን አንባቢ እጋብዛለሁ ። በገጽ 119-20 የሠፈሩትን ሃሳቦች በጥሞና እንዲመለከቷቸው የሚያስፈልጉ ናቸው ። ካፒታሊስቶችና ወደነሱ ከድተው የተጠጉት ሶሻል ትምክህተኞች (ካውትስኪ እጿም በሌለው አኳኋን የሚቃወማቸው) ግዛት መደረብን በሚመለከት ረገድ ምን ያህል ሀፍረተቢስ ዋሾዎች እንደሆኑ ፣ ሣንሱሮች ሊረዱት በማይችሉበት አኳኋን ፣ ለአንባቢ ለማሣየት ፣ ካፒታሊስቶቻቸው የሚያደርጉትን የግዛት መጠቃለል ጉዳይ ምን ያህል ሀፍረተቢስ በሆነ መንገድ ሊከልሉ እንደሚሞክሩ ለማሣየት ጃፓንን እንደምሣሌ ለመጥቀስ ተገድጄ ነበር ። ጥንቁቁ አንባቢ ሩሲያን ለጃፓን እና ፊንላንድን ፣ ፖላንድን ፣ ኩርላንድን ፣ ዩክሬይንን ፣ ኪቫን ፣ ቦካራን ፣ ኢስቶንያን ፣ ወይንም ሌላ የታላቁ ሩስያውን ያልሆኑ ልዝቦች የሚኖሩበትን አካባቢ ለኮርያ በቀላሉ መተካት ይችላል ።

ይህ መጽሔት ፣ ለአንባቢው ፣ የኢምፔሪያዝም ኤኮኖሚያዊ ጽንሰ ሀሣብ የሆነውን የምጣኔ ሀብታዊ መሠረት ጥያቄ ለመረዳት ያስችለዋል ብዬ እገምታለሁ ። ምክንያቱም የኤኮኖሚው ጥናት ካልተጠናቀቀ የዘመናዊውን ጦርነትና ፖለቲካ ለመገንዘብ አይቻልምና ነው ።

ደራሲው

ፔሬትሮግራድ ሚያዝያ 26.1917

# መ ግ ቢ ያ

## ለፈረንሣዩና ለጀርመኑ እትሞች

## I

በሩሲያውኛው እትም መግቢያ ውስጥ እንደተገለጠው ሁሉ ይህ መጽሔት በ1916 የዛሪስቱን ሣንሱር እያሰብኩ ነበር የተጻፈው ። በአሁኑ ጊዜ ጠቅላላውን መጽሐፍ ለመከለስ አልቻልኩም ፤ ተገቢም መስሎ አልታየኝም ፤ ምክንያቱም የመጽሐፉ ዋና ዓላማ የነበረው ፤ አሁንም ነው ፤ አሌ በማይባለው የቡርዧ ስታቲስቲክስ የተጠቃለለ መደበኛ ዘገባና የሁሉም ሀገሮች ቡርዧ ምሁራን አምነው በሚቀበሉት ላይ ተመሥርቶ የዓለም ካፒታሊስት ሥርዓትን በዓለም አቀፋዊ ግንኙነቶቹ በሃያኛው ምዕተ ዓመት መግቢያው ላይ — በመጀመሪያው የኢምፔሪያሊስት ጦርነት ዋዜማ ማለት ነው — ያለውን የተጠናቀረ ሥዕል ለማቅረብ ነው ።

በመጠኑም ቢሆን ፤ በሠለጠኑ የካፒታሊስት ሀገሮች ውስጥ ለሚገኙ ኰሚዩኒስቶች ፤ በዚህ ከዛሪስቱ ሣንሱር በኩል ሲታይ ሕጋዊ በሆነው መጽሔት አማካይነት እንበል በቅርብ ጊዜ ከተፈጸመው የኰሚዩኒስቶች ጅምላ መታሠር ወዲህ በአሁኑ ወቅት በአሜሪካና በፈረንሣይ ያሉ ኰሚዩኒስቶች ሊጠቀሙባቸው የሚችሉ ፤ የሚገባቸውም የሕጋዊነት እንጥፍጣፊዎች መኖራቸውን በማሣየት የሕብረተሰብ እርቅ ፈላጊዎችን አመለካከትና « ለዓለም አቀፋዊ ዲሞክራሲ ያላቸውን ተስፋ » ፍጹም ስህተትኛነት ለመግለጽ እንዲችሉ እምነት ሊያሳድርባቸው ስለሚችል ይጠቅማቸዋል ። በሣንሱር ውስጥ ባለፈው መጽሔት ውስጥ ሊጨመሩ የሚገባቸውን በጣም ጠቃሚ የሆኑትን ሀሣቦች በዚህ መግቢያ ውስጥ አስፍሬአቸዋለሁ።

# II

የ1914—18 ጦርነት II በሁለቱም ወገኖች በኩል የኢ ምፔሪያሊስት /ማለትም የግዛት ማጠቃለል ፤ የመበዝበዝ ፤ የዘረፋ ጦርነት/መሆኑ በዚህ መጽሔት ውስጥ ተረጋግ ጧል ። ዓለምን የመከፋፈል ፣ ቅኝ ግዛቶችንና ገንዛባዊ ወረት /የፊናንስ ካፒታል/ ፤ የተጽዕኖ አካባቢ ፤ ወዘተ የመ ቀረማመትና መልሶ የመቀረማመት ጦርነት ነው ።

የጦርነቱ ትክክለኛ ኅብረተሰብአዊ ወይንም ትክክ ለኛ መደባዊ ጠባይ ፣ በጦርነቱ ዲፕሎማሲያዊ ታሪክ ሣይ ሆን በሁሉም ጠብ ጫሪ ሀገሮች ከሚገኙት የገዥ መደ ቦች ነባራዊ አቀማመጥ ትንታኔ የሚገኝ መሆኑ ሀቅ ነው። የነባራዊውን አቀማመጥ ለመገመት የተነጣጠሉ መረጃ ዎችን (የህብረተሰብ ኑሮ ክስተት አለመጠን የተወሣሠበ ከመሆኑ የተነሣ ለሚቀርበው ሀሣብ ሁሉ ማረጋገጫ የተ ፈለገውን ያህል ምሣሌዎች ወይንም መረጃዎች መምረጥ ይቻላል) ወይንም ምሣሌዎችን ብቻ ሣይሆን የሁሉንም ጠብ ቆስቋሽ ሀገሮችና የጠቅላላውን ዓለም ምጣኔ ሃብ ታዊ ሕይወት ጠቅላላ መረጃዎችን መውሰድ ያሻል ። የነ ዚህን ዓይነቶች አሌ ሊባሉ የማይችሉ የተጠቃለሉ መረ ጃዎችን ነው ። በ1876 እና በ1914 የተፈጸመውን የዓለምን መቀረማመት ለመግለጽ (ምዕራፍ 6 ውስጥ) የዓለምን የባ ቡር መሥመሮች በ1890 እና በ1913 መከፋፈል (ምዕራፍ ሰባት) ለመግለጽ የተጠቀምኩት ። የባቡር መሥመሮች መሠረታዊ የካፒታሊስት ኢንዱስትሪዎች ማለትም የከሰል፣ የብረትና የአረብ ብረት ጥርቅሞች ፣ ጥርቅሞችና ጉል ተው የሚታዩ የዓለም ንግድና የቡርዧ ዲሞክራቲክ ሥል ጣኔ መስፋፋት አመልካች ናቸው ። የባቡር መሥመ ሮች ከከፍተኛ ደረጃ ኢንዱስትሪ ፣ ከሞኖፖሊዎች ፣ የሸቀጥ ማከፋፈያ ድርጅቶች ፤ ከሲንዲኬቶች ፤ የም

ርት ውጤቶች ፣ የእቃ ዋጋዎች ፣ ገበያ ወዘተ . . . የሚ ቆጣጠሩ የንጋዴዎችና የፋብሪካ ባለንበረቶች ቅንጅት (ካርቴይል) ከትረስቶች፣ ከባንኰችና ከገንዘባዊ ስልጣን /ፋይናንስ ኦሊጋርኪ/ ጋር እንዴት እንደተያያዙ በሚከተ ሉት የመጽሐፉ ምዕራፎች ውስጥ ተመልክቷል ። ያልተ ስተካከለው የባቡር መሥመሮች ክፍፍል ፣ ያልተስካከ ለው ዕድገታቸው በዓለም አቀፍ ደረጃ የዘመኑን ሞኖፖ ሊያዊ ካፒታሊዝም አጠቃሎ ያቀርባል ። ይህም ማጠቃ ለያ ፣ በምርት ውስጥ የግል ባለንብረትነት እስካለ ድረስ በእንደዚህ ያለው ምጣኔ ሀብታዊ ስርዓት ውስጥ የኢምፔ ሪያሊስት ጦርነቶች ሳይታለሙ የተፈቱ መሆናቸውን ያረጋግጣል ።

የባቡር መሥመሮች መዘርጋት ፣ ቀላል መሆን ያለ በት ፣ ግልጽ ዲሞክራሲያዊ ፣ ባህላዊና የሥልጣኔ በር ከፋች ተቋም ይመሥላል ። የካፒታሊስትን የባርያ አገዛዝ በብሩህ ቀለም እንዲያቀልሙ በሚከፈላቸው የቡርዧ ምሁ ራንና በንዑስ ከበርቴ ጋጠወጦች አስተሣሰብ ሊሆን ይች ላል ። እንደእውነቱ ከሆነ በሺህ የተለያዩ ውስብስቦች እነዚህን ተቋሞች በምርት መገልገያ ውስጥ ካለው የግል ባለንብረትነት ጋር በአጠቃላይ የሚያስተሳስሩት የካፒ ሊስት ክሮች ፣ ይህን የባቡር መሥመር መዘርጋት ለሺህ ሚሊዮን ሕዝብ መጨቆኛ (በቅኝ ግዛቶችና በከፊል ቅኝ ግዛቶች ውስጥ) ማለትም ጥገኛ ሀገሮች የሚኖሩበትን ከግ ማሽ በላይ የዓለምን ሕዝብና « በሠለጠኑት » ሀገሮች ያሉትን የወረት ደመወዝተኛ ባሪያዎች መጨቆኛ ወደ ማድረጉ ለውጦታል ።

በአነስተኛ ባለሀብቶች ወዝ ላይ የተመሠረተ የግል ንብረት ፣ ነጻ ውድድር ፣ ዲሞክራሲ ፣ ሌሎችም ካፒታሊ

ስቶችና ጋዜጦቻቸው ሠራተኛውንና ገበሬውን የሚያታ ልሉባቸው ማወናበጃ ቃላቶች ሁሉ እየተረሱ ሄደዋል ። ካፒታሊዝም እፍኝ የማይሞሉ « የሠለጠኑ » ሀገሮች ቄጥሩ ይሀ ነው የማይባለውን አብዛኛውን የዓለም ሕዝብ በቅኝ ግዛታዊ ጭቆና ስር ወደሚያውሉበት ገንዘባዊ ማን ቆንት ዓለም አቀፋዊ ሥርዓት እያደገ መጥቷል ። «የተዘረ ፈውንም ሀብት» ሁለት ወይንም ሶስት እስከ ጥርሣቸው ድረስ የታጠቁ ፣ (አሜሪካ ፣ ታላቋ ብሪታንያ፣ ጃፓን) ይከ ፋፈሉታል።እነሱ ዘረፋውን ለመከፋፈል ወደሚያስነሱት ጦርነት መላውን ዓለም የሚከቱ ፣ ኃይለኞች ዓለም አቀፍ ዘራፊዎች ናቸው ።

III

በጀርመን ንጉሣዊ መንግሥት ትዕዛዝ ስምምነት የተደረሰበት የብሬስት ሊትቮስክ ውልና ከዚያም በኋላ የወጣው አራዊታዊና የተወገዘው ፤ በአሜሪካንና በፈ ረንሣይ ሪፑብሊኮችና በነፃዬቱ እንግሊዝ ትእዛዝ ስምም ነት የተደረሰበት የቨርሣይልሱ ውል ራሳቸውን ጸረ ጦር ነትና ሶሻያሊስት እያሉ ቢጠሩም እንኳን ሠላምና ጥገ ናዊ ለውጥ በኢምፔሪያሊዝም ውስጥ ይቻላል ብለው የሚሟገቱትን ፣ ዊልሡኒዝምን የሚያወድሱትን፣ የኢም ፔሪያሊዝምን የብዕርና የንዑስ ከበርቴ ጸረ ተራማጅ ቅጥ ረኛ ኩሊዎች በማጋለጥ ለሠው ልጅ በጣም ጠቃሚ አገ ልግሎት ሠጥተዋል ።

ከጀርመን ወይንም ከእንግሊዝ ገንዘባዊ ዘራፊዎች የትኛው የዝርፊያውን ድርሻ ይበልጥ እጅ እንደሚያገኝ ለመወሰን በተደረገው ጦርነት ማለትም በአሥር ሚሊ ዮን ለሚቆጠር ሕዝብ መጥፊያና አካለ ስንኩል መሆን ምክንያት የሆነው ጦርነትና ከላይ የጠቀስናቸው ውሎች፤ በቡርዧው የተረገጡትን ፤ የተጨቆኑትን ፤ የተታለሉ ትንና የተጭበረበሩትን በብዙ ሚሊዮን የሚቆጠሩትን

ሕዝቦች ዓይኖች ተደርጐ በማይታወቅ ፍጥነት እየከፈቱ ናቸው ። ስለሆነም ጦርነቱ ካደረሰው አለም አቀፍ ጦር ነት ውስጥ ፣ የሒደቱ ደረጃዎች ምንም ያህል አድካሚና የተራዘሙ ቢሆኑም ካለ ወዝ አደሩ አብዮትና ብሎም የሱ ድል ፣ መቆሚያ የሌለው ፣ ዓለም አቀፋዊ አብዮታዊ ቀውስ እየተፈጠረ ነው ።

በ1912 ዓ. ም. ለጦርነት በአጠቃላይ ሣይሆን/ ጦር ነቶች የተለያዩና አብዮታዊ ጦርነትንም ይጨምራሉና/ በተለይ በ1914 ዓ.ም. ለተጀመረው ጦርነት አድናቆቱን ያበረከተው የሁለተኛው ዓለም አቀፍ የባስል መግለጫ /ማኒፌስቶ/ አሁን የሁለተኛውን ዓለም ዓቀፍ ጀግናች ሀፍረተቢስ ክስረትና ሽፍጥ ሙሉ በሙሉ የሚያጋልጥ ሀውልት ሆኗል ። ስለዚህ ነው መግለጫውን ለአሁኑ እትም 4 በአባሪነት እንደገና መልሼ ያወጣሁትና አን ባቢውን ደግሜ ደጋግሜ የሁለተኛው ዓለም አቀፍ ጀግ ኖች በዚህ ማኒፌስቶ ውስጥ ያሉትን ፣ በሚይቀረው ጦር ነትና በወዝ አደሩ አብዮት መካከል ስላለው ግንኙነት በትክክልና ግልጽ ባለ መንገድ የሚያወሱትን ሀሣቦች ልክ ሌባ ሰርቆ የፈጸመበትን ሥፍራ እንደሚሸሸው ሁሉ እነሱም የሚሸሿቸው መሆኑን እንዲገነዘብ የምጠይቀው።

IV

በዚህ መጽሔት ውስጥ ፣ በየሀገሩ የታወቁ ንድፈ ሀሣባውያን የሁለተኛው ዓለም አቀፍ መሪዎች (ካኡ ቶስኪና ተከታዮቹ በአውስትሪያ ፣ ሬምሲ ማክዶናልድና ሌሎችም በእንግሊዝ ፣ አልበርት ቶማስ በፈረንሣይ ወዘተ) እኛ አያሌ ሶሺያሊስቶች ፣ ጠጋኞች ፤ እርቅ ፈላጊዎች ፤ የቡርዧ ዲሞክራቶችና ቀሣውስቶች ፣ ወክለውት ስለ ሚገኘው ዓለም አቀፋዊው የርዕዮተ ዓለም መሥመር ፣ ግለ ትም ስለካውትስኪዝም የተለየ አስተያየት ተደርጐበታል ።

ይህ የርዕዮተ ዓለም መሥመር ፥ ባንድ በኩል የሁ ለተኛው ዓለም አቀፍ መበስበስና መፈራረስ ውጤት ሲ ሆን ፥ በሌላ ወገን ደግሞ ጠቅላላ የኑሮአቸው ሁኔታን የቡ ርዧና የዲሞክራቲክ ዓምልኰ ተገዥ ያደረጉት የንዑስ ከበርቴዎች ርዕዮተ ዓለም የማይቀረው ውጤት ነው ።

የኰትስኪና የመሠሎቹ አመለካከት ፥ ኰትስኪ ራሱ ለብዙ ዘመናት የታወቀበትንና ሶሺየሊስት አድር ባይነትን/ የበርንስቴይን ፤ የሚለራንድን ፤ የሂንድ ማንን ፤ የጉምፐርዘን ፤ ወዘተ/ የተዋጋባቸውን እነዚያኑ የማርክሲ ዝሃን አብዮታዊ መርሐ ግብሮች ፥ የሚያወግዝ ነው ። ስለዚህ በዓለም ዙሪያ ያሉ የኰትስኪ ተከታዮች በተግባ ራዊ ፖለቲካ ከመጨረሻ አድርባዮች ጋር/በሁለተኛው ወይንም ከሀዲው ዓለም አቀፍ በኩል/ እና የቡርዧ አስተዳ ዳሪዎች ጋር/ ሶሺያሊስቶች በሚካፈሉበት በቡርዧ ጥምር አስተዳደሮች በኩል/ ቢዋሀዱ አጋጣሚ ሊሆን አይች ልም ።

እያደገ ያለው ዓለም አቀፍ የወዝ አደር አብዮታዊ ንቅናቄ በአጠቃላይ የኰሚዩኒስት ንቅናቄ በተለይ የኰ ትስኪዝምን ንድፈ ሀሣባዊ ስህተቶች ሣይተነትኑና ሣያ ጋልጡ ሊቀሩ አይችሉም ። በተለይም ሠላማዊነትና «ዲሞ ክራሲ » በአጠቃላይ ከማርክሲዝም ምንም ዓይነት ዝም ድና ሳይኖራቸው ፤ ግን እንደኰትስኪና ተከታዮቹ ፤ የኢምፔሪያሊዝምን ቅራኔዎች ሥር መስደድንና የሱ ውላ ጅ የሆነውን የማይቀረውን አብዮታዊቀውስ የሚያጨ ልሙት ፤ አሁንም በዓለም ላይ ተስፋፍተው ስለሚገኙ ፤ እነ ዚህን አዝማማያዎች የመዋጋቱ የሞራል ግዴታ ፤ ቡር ዧው አጭበርብሮ የሚጠቀምባቸውን አነስተኛ ባለን ብረቶችን በሚሊዮን የሚቆጠረውንና ከሞላ ጉደል የን

ውስ ከበርቴውን አይነት ኑሮ የሚኖረውን ሠራተኛውን ሕዝብ ከገሎኑ ማሠለፍ ያለበት የወዝ አደሩ ፓርቲ ነው ።

V

በምዕራፍ 8 ውስጥ ስለ « የካፒታሊዝም ጥባቴ ነትና መበስበስ » በተጻፈው ላይ አጭር አስተያየት መስ ጠት ያስፈልጋል ። በጽሑፉ እንደተጠቀሰው ሁሉ ፤ ሂላ ፈርዲንግ ፤ የቀድሞ « ማርክሲስት » ፤ የአሁኑ የኰትስኪ የትግል ጓድና በነጻው የጀርመን 5 ሶሺያል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ዋንኛው የቡርዣው ጠጋኝ ፖሊሲ ወኪል ፤ በግ ልጽ እርቅ ፈላጊና ጠጋኝነቱን ካሣወቀው የእንግሊዙ ሆብሶን ጋር ሲወዳደር ፤ በዚህ ጥያቄ ላይ አንድ እርምጃ ወደኋላ ቀርቷል ። በአሁኑ ጊዜ በመላው ሠራተኛው መደብ ውስጥ ያለው ንቅናቄ በዓለም አቀፍ ደረጃ ከሁ ለት መከፈሉ ጉልህ ሆኗል ። /ሁለተኛውና ሶስተኛው ዓለም አቀፎች/ በሁለቱ መሥመሮች መካከል የትጥቁ ትግልና የእርስ በርስ ጦርነቱ መፋፋም ሀቅ እየገሎላ ሄዷ ል ። ሜንሼቪኰችና ሶሺያሊስት አብዮታውያን ፥ በቮ ልሼቪኰች ላይ ለሚያደርጉት ተቃውሞ ፤ ለከልቻክና ለዴንኪን የሚመጣው እርዳታ ፤ በጀርመን ስፓርታሲስ ቶችን 6 በመቃወም ሼይዴማንስና ኖስከስ ከቡርዧው ጋር በማቀነባበር የሚያካሒዱት ትግል ፤ ተመሣሣይ ሁና ቴዎች በፊንላንድ ፤ በፖላንድ ፤ በሀንጋሪ ፤ ወዘተ —የዚህ ያለም ታሪካዊ ክስተት ምጣኔ-ሀብታዊ መሠረት ምንድነው ?

በትክክል የካፒታሊዝም ጥባቴነትና መበስበስ ፣ ከፍተኛ የታሪካዊ የዕድገት ደረጃ ጠባዩ ማለትም ኢም ፔሪያሊዝም ነው ። ይህ መጽሐፍ እንደሚያሣየው ፤ ካፒ ታሊዝም ፤ እፍኝ የሚሆኑ (ከዓለም ፏሪዎች አንድ አሥ ረኛ ያነሱ ፤ «በለጋሽ» ፥ እና በለዘብተኛ ግምት ከአንድ አምስተኛ የሚያንሱ) ዓለምን « ኩፓን በመቁረጥ » ብቻ

የሚያርፉ አለመጠን ባለጸጎችና ኃያላን የሆኑ መንግሥታትን መርጦ አውጥቷል ። ከጦርነቱ በፊት በነበረውትመንና በቅድመ ጦርነቱ ወቅት በነበረው የቡርዧ ስታቲስቲክስ መሠረት የወረት ወደውጪ መላክ ከስምንት እስከ አሥር ሺህ ሚሊዮን ፍራንክ በዓመት ገቢ ያስገኛል ። በእርግጥም አሁን የበለጠ ያስገኛል ።

ከዚህ ከመጠን በላይ ከሆነ ከፍተኛ ትርፍ/ ካፒታሊስቶች « ከራሳቸው » ሀገር ወዝ አደሮች ከሚያንጠፉጥፉት ትርፍ በላይ የተገኘ በመሆኑ/ በርግጥም የወዝ አደር መሪዎችንና የወዝ አደር መሳፍንት የላይኛውን ክፍል መደለያ ጉቦ የሚሠጥ ማግኘት ይቻላል ። « የሠለጠኑት» ሀገሮች ካፒታሊስቶችም ይህንኑ ነው የሚያደርጉት ፤ በሺህ የተለያዩ መንገዶች በቀጥታ ወይንም በተዘዋዋሪ ፤ በግልጽ ወይንም ውስጥ ለውስጥ ጉቦ ይሰጧቸዋል ።

ሠራተኛው ወደቡርዧነት የተለወጠበት ፤ ወይንም በአኗኗራቸው ሥልት፣በገቢያቸው መጠንና በጠቅላላ ዓመለካከታቸው ፍጹም ጋጠ ወጥ የሆኑ የወዛደር መሳፍንታዊነት ደረጃ ፤ ዋነኛው የሁለተኛው ዓለም አቀፍ ምሰሶ በአጊዜያችን ደግሞ ዋነኛው ህብረተሰብአዊ (ወታደራዊ አይደለም) የቡርዧው ምሰሶ ነው ። ምክንያቱም እነሱ በሠራተኛው መደብ ንቅናቄ ደንበኛ የቡርዧው ወኪሎች ፤ የካፒታሊስቱ መደብ የወዛደር መደብ መኮንኖች ፣ የጠጋኝነትና የጅብደኝነት ትክክለኛ ጸዋሬዎች ናቸውና።በወዝ አደሩና በቡርዧው መካከል ለሚደረገው የእርስ በርስ ጦርነት ከነሱ መካከል ቁጥራቸው ያነሰ ከቡርዧው ጐን መሠለፋቸው የማይቀር ነው፤ማለትም የ « ቨርሣሌዎ » ና የ« ኰሚዩናርድስ » ግጭት ።

የዚህን ክስተት ምጣኔ ሀብታዊ ሥረ መሠረት ካልተረዳንና የሶሺያልና የፖለቲካዊ ምንነቱን ካልተገነ

ዘብን ፤ ለኰሚዩኒስት ንቅናቄና ለማይቀረው የሕብረተሰብ አብዮት ተግባራዊ ችግሮች መፍትሔ ለማግኘት አንድም እርምጃ መራመድ አይቻልም ።

ኢምፔሪያሊዝም የወዝ አደሩ የህብረተሰብ አብዮት ዋዜማ ነው ። ይህም ከ1917 ዓ. ም. ጀምሮ በዓለም አቀፍ ደረጃ ተረጋግጧል ።

ሐምሌ 6 ቀን 1920 ዓ. ም.

ኤን ሌኒን

ባለፉት አሥራ አምስትና ሃያ አመታት ውስጥ ፤ በተለ ይም ከስፓኝ አሜሪካን /1898/ እና ከአንግሎ ዳች (1899-1902/ ጦርነቶች ጀምሮ ምጣኔ ሀብታዊውና በተጨማ ሪም ፖለቲካዊው ሥነ ጽሑፍ ፤ የአሁኑን ወቅት ለመግ ለጽ ፥ « ኢምፔሪያሊዝም » የሚለውን ቃል በይበልጥ በተደጋጋሚ ሲጠቀሙበት ይታያል ። በ1902 ፥ በእንግ ዛዊው ኤኮኖሚስት ፥ በጄ. ኤ. ሆብሶን የተደረሰ ፥ ኢም ፔሪያሊዝም የሚል መጽሐፍ ፥ ለንደንና ኒው ዮርክ ውስጥ ታትሞ ወጥቶ ነበር ። አመለካከቱ ፥ የኅብረተሰብ ጠጋ ኝነትና እርቅ ፈላጊነት የሆነ ፤ ይህም ደግሞ በጽንሰ ሀሣቡ ከቀድሞው ማርክሲስት ከካርል ኮትስኪ አንድ አይነት የሆነው ደራሲ ፤ ስለኢምፔሪያሊዝም ፤ ዋና ዋና ፤ ለየት ያሉ ምጣኔ ሀብታዊና ፖለቲካዊ ባህርያት ፤ በጣም ጠቃሚና የተቀነባበረ መግለጫ ሰጥቷል ። በ1910 ዓ. ም. የአውስትሪያኑ ማርክሲስት ፤ የሩዶልፍ ሂልፈርዲንግ ገንዘባዊ ወረት በቪየና ታትሞ ወጥቶ ነበር /የሩሲያ እትም ሞስኮ 1912/ ። ይህ ደራሲ ፥ የገንዘብን ንድፈ ሀሳብ በሚ መለከት ረገድ ስህተት ቢፈጽምም ፤ በበኩሉ አድርባይ ነትን ከማርክሲዝም ለማስታረቅ አንዳንድ አዝማሚያ ቢያሣይም ፤ ጽሑፉ ስለ « የካፒታሊስት ዕድገት የመጨ

ረሻው ደረጃ » ይህም የመጽሐፉ ንዑስ ርዕስ ነው ፤ በጣም ጠቃሚ ንድፈ ሐሣባዊ ትንተና ይሠጣል ። በእርግጥ ፤ ስለኢምፔሪያሊዝም ባለፉት ጥቂት አመታት የተነገረው ፤ በተለይም በአያሌ መጽሔታዊና ጋዜጣዊ ጽሑፎችና በተጨማሪም በውሣኔዎች ፤ ለምሣሌ የ1912 ዓ. ም. ሀጋይ ወራት ውስጥ ተደርጎ የነበረው የቸምኒትዝና ባስል ኮን ግሬስ ፤ በነዚህ ከላይ በተጠቀሱት ሁለት ድራሲያን ከተ ተነተኑት ፤ ወይንም በትክክል ለመናገር ተጠቃለው ከቀ ረቡት ሀሣቦች እምብዛም አይወጣም ። ወደኋላ ላይ ፤ ባጭ ሩና በተቻለ መጠን ቀለል ባለ መንገድ ፤ በዋና ዋና የኢ ምፔሪያሊዝም ምጣኔ-ሃብታዊ ባህርያት መካከል ያሉትን ዝምድናና ግንኙነቶች ፤ ለማቅረብ እሞክራለሁ ። ምንም ያህል መጠቀስ የሚገባቸው ቢሆኑም ፤ ምጣኔ ሀብታዊ ያልሆኑትን ገጾቹን ለመጥቀስ አልችልም ፤ በመጽሐፉ መጨረሻ ላይ ፤ ሁሉም አንባቢያን ላይ ፈልጓቸው ይች ላሉ ፣ ጥቅስ የተወሠደባቸው ሥነ ጽሑፎችና ሌሎች ማስ ታወሻዎች ቀርበዋል ።

## ምዕራፍ አንድ

# የምርትና የሞኖፖሊዎች መድለብ

የኢንዱስትሪ በከፍተኛ ደረጃ ማደግና ምን ጊዜም ታላላቅ በሆኑ ድርጅቶች ውስጥ ከዚህ በፊት ባልታየ የፍ ጥነት ሂደት የምርት መከማቸት ፤ ዋነኛ ከተባሉት የካ ፒታሊዝም መለያ ባሕርያት ውስጥ ናቸው ። ስለዚህ ሂደት ፤ ዘመናዊ የምርት ቁጥጥር የተሟላና ትክክለኛ ማስረጃዎች ይሰጣል ።

በጀርመን ፤ ለምሣሌ ፤ ከእያንዳንዱ 1.000 ኢንዱ ስትሪያዊ ድርጅቶች መሀል ፣ ትልልቅ ድርጅቶች ፤ ማለ

ትም ከ50 በላይ ሠራተኞች የሚቀጥሩ ፤ በ1882 ዓ. ም ሶስት ፥ በ1895 ዓ. ም ስድስት እና በ1907 ዓ. ም. ደግሞ ዘጠኝ ነበሩ ። በተጨማሪም ከእያንዳንዱ ተቀጣሪ 100 ሠራተኛ መሀል የእነዚህ ድርጅቶች ቡድን ፤ ከላይ በተ ጠቀሱት ዓመተ ምሕረቶች 22 ፤23 ፤ እና 37 ሠራተኞች በተከታታይ ቀጥረው ነበር ። የም ሆኖ በትልልቅ ድርጅ ቶች ውስጥ ያለው ወዝ አደር የበለጠ አምራች ከመሆኑ የተ ነሣ ከሠራተኞች ክምችት ይልቅ የምርት ክምችት ከፍ ተኛ ነበር ። ይህንንም ከእንፋሎት ኢንጅኖችና ከኤሌክ ትሪክ ሞተሮች አኀዞች ማየት ይቻላል ። በጀርመን ፤ በአ ጠቃላይ አነጋገር ኢንዱስትሪ ተብሎ የሚጠራውንና ንግ ድን ማጓጓዣን ፤ ወ. ዘ. ተ. የሚያጠቃልለውን ብንወስድ የሚከተለውን አቋም ይዞ እናገኘዋለን ። ከፍተኛ ደረጃ ያላቸው ድርጅቶች ፤ ከጠቅላላው 3,265,623 ውስጥ 30, 588 ማለትም 0.9 እጅ ከመቶ ናቸው ። እነዚህ ድርጅቶች ከጠቅላላው 14,400,000 ሠራተኛ ውስጥ 5,700,000 ውን ማለትም 39.4 እጅ ከመቶውን ይቀጥራሉ ። ከጠቅ ላላው 8,8000,00 የእንፋሎት የፈረስ ጉልበት መሀል 6,600, 000 ውን ማለትም 75.3 እጅ ከመቶ እና ከጠቅ ላላው 1,500,000 ኪሎዋት ኤሌክትሪክሲቲ መሀል 1,200,000 ውን ማለትም 77. 2 እጅ ከመቶ ይጠቀማሉ።

ከጠቅላላው ድርጅቶች አንድ መቶኛ የሚሆኑት ከጠቅላላው የእንፋሎትና የኤሌክትሪክ ኃይል ከሶስት አራተኛ እጅ የበለጠውን አገልግሎት ላይ ያውላሉ ። ሁለት ሚሊዮን ዘጠኝ መቶ ሰባ ሺህ ትንንሽ ድርጅቶች /እስከ አምስት ሰው የሚቀጥሩት/ ከጠቅላላው 91 እጅ በመቶ የሚሆኑት ማለት ነው ፤ ከጠቅላላው የእንፋሎትና የኤሌክትሪክ ኃይል 7 እጅ በመቶውን ብቻ አገልግሎት ላይ ያውላሉ ። በአሥር ሺህ የሚቆጠሩ ግዙፍ ድርጅቶች

ሁሉንም ነገር ማድረግ ሲችሉ ፤ በሚሊዮን የሚቆጠሩት ትንንሾቹ ደግሞ ምንም ርባን የላቸውም ።

በ1907 ዓ. ም. በጀርመን ሀገር 586 ተቋሞች አንድ ሺህና ከዚያም የበለጡ ከጠቅላላው የኢንዱስትሪ ተቀጣ ሪዎች ወደ አንድ አሥረኛ የሚደርሱ (1,380,000) ሠራ ተኞች ቀጥረው የሚያሠሩ ሲሆን ከጠቅላላው የእንፋሎ ትና የኤሌክትሪክ ኃይል ወደ አንድ ሶስተኛ /32 እጅ ከ መቶ/ የሚሆነውን አገልግሎት ላይ ያውላሉ[1] ። የጥሬ ገን ዘብ ወረትና ባንኮች ይህን እፍኝ የማይሞሉ ታላልቅ ድር ጅቶች የበላይነት እንደ ቃሉ አባባል ከሆነ አሁንም ይበ ልጥ የተሟላ ያደርጉታል ፤ ማለትም በሚሊዮን የሚቆ ቆጠሩ አነስተኛ ፤ መካከለኛና እንዲያውም አንዳንድ ትላ ልቅ « ባለንብረቶች » ሙሉ በሙሉ በመቶ የሚቆጠሩ የጥቂት በሚሊዮን የሚቆጠር ገንዘብ ያከማቹ ባላሀብ ቶች ያደርጓቸዋል ።

ዘመናዊ ካፒታሊዝም ባለበት በሌላው በተራመደ ሀገር ፤ በአሜሪካ ፤ የምርት ክምችት ዕድገት አሁንም ከፍ ተኛ ነው ። እዚህ ስታቲስቲኮች ኢንዱስትሪን ነጥለው በቃሉ ጠባብ አጠቃቀም በማውጣት ድርጅቶችን በዓ መት በሚያመርቱት ዋጋ መጠን ይመድቧቸዋል ። በ19 04 ዓ. ም የአንድ ሚሊዮን ዶላርና ከዚያም በላይ የሚገ መት ምርት የሚያመርቱት ከ1,900 (ከ216,180 ውስጥ ማለትም 0.9 እጅ ከመቶ) በላይ ይቆጠሩ ነበር ። እነዚ ህም 1,400,000 ሠራተኞችን (ከጠቅላላው 5,500,000 ሠራተኛ ማለትም 25.6 እጅ ከመቶ) የቀጠሩና ያመት የም ርት ውጤታቸው ደግሞ 5,600,000,000 (ከጠቅላላው 14,800,000,000 38 እጅ ከመቶ) የሆኑ ናቸው ። ከአም ስት ዓመት በኋላ ፤ በ1909 ዓ. ም. እነዚህ አኀዞች ፤ 3,060 ድርጅቶች (ከጠቅላላው 268,491 ድርጅቶች

1.1. እጅ በመቶ) የቀጠሩት ሠራተኛ ቁጥር 2,000,000 (ከመላው 6,600,000 ሠራተኛ 30.5 እጅ ከመቶ) ያመት የምርት ውጤታቸው 9,000,000,000 (ከጠቅላላው 20,7000,000,000 43,8 እጅ ከመቶ) ሆነዋል[2] ።

ከጠቅላላው የሀገሪቱ ድርጅቶች የምርት ውጤት ወደ ግማሽ የሚያህለው በነዚህ ድርጅቶች አንድ መቶኛ ክፍል የሚመረት ነበር ። እነዚህ 3000 ግዙፍ ድርጅቶች 258 የኢንዱስትሪ ቅርንጫፎችን ያቅፋሉ ። በተወሰነ የዕድገት ደረጃው ፤ ከምችት ራሱ ፤ ወደ ሞኖፖሊ እንደሚያመራ ከዚህ መረዳት ይቻላል ፤ ምክንያቱም 20 የሚሆኑ ግዙፍ ድርጅቶች በቀላሉ ስምምነት ላይ መድረስ ሲችሉ በሌላ በኩል ደግሞ ለውድድር እንቅፋት መሆን ፤ የሞኖፖሊ አዝማሚያ ከነዚሁ ድርጅቶች መጠኖች የሚመነጭ ስለ ሆነ ይህ የውድድር ወደ ሞኖፖሊ መለወጥ የዘመኑ ካፒ ታሊስት ምጣኔ-ሃብት በጣም ጠቃሚ ከሆኑት ክስተቶች ይበልጥ ከፍተኛው ባይሆንም ከአቢዮቹ አንዱ በመሆኑ ሠፋ ባለ አኳኋን ልንመረምረው ይገባል ። ነገር ግን በቅድሚያ ሊኖር የሚችል አንድ አለመግባባት ግልጽ መሆን አለበት።
ለእያንዳንዱ የኢንዱስትሪ ቅርንጫፍ በደርዘን ብቻ

የሚቆጠሩ ከፍተኛ ድርጅቶች ያሉ ይመስል የአሜሪካ ስታቲስቲክስ የሚያወራው በ250 የኢንዱስትሪ ቅርንጫ ፎች ውስጥ ስለ 3000 ግዙፍ ድርጅቶች ነው ።

ጉዳዩ ግን ይህ አይደለም ። በማናቸውም የኢንዱ ስትሪ ቅርንጫፍ ትልልቅ ድርጅቶች የሉም ፤ ከዚ ህም በላይ ፤ በካፒታሊዝም ከፍተኛ የዕድገት ደረጃ ፤ የምርት ቅንጅት በመባል የሚታወቅ አንድ በጣም ጠቃሚ ባሕርይ አለ ። ይህም ማለት ወይ በተከታ ታይ ያለውን የጥሬ ዕቃዎች ለምርት የማዘጋጀት ሂደት

(ፕሮሲሲንግ) (ለምሣሌ የብረትን ንጥረ ነገር ወደ ጥቅል ብረት ማቅለጥ ፤ ጥቅል ብረትን ወደ አረብ ብረት ፤ ከዚ ህም በኋላ ምናልባት የአረብ ብረት ዕቃዎችን ማምረት) የሚወክሉ ወይንም አንዱ ለሌላው ረዳት የሚሆኑ /ለም ሣሌ ቁርጥራጮችን ወይንም ተጨማሪ ውጤቶችን ጥቅም ላይ ማዋል ፤ መጠቅለያዎችን ማምረት፤ ወ.ዘ.ተ/ልዩ ልዩ የኢንዱስትሪ ቅርንጫፎችን ወደ አንድ ነጠላ ድርጅት መመደብ ማለት ነው ።

« ቅንጅት » ይላል ሂልፈርዲንግ ሲጽፍ « የንግድን ውጣ ውረድ ያስተካክላል ፤ ስለሆነም ለተቀናጁት ድር ጅቶች ይበልጥ የረጋ የትርፍ ደረጃን ያረጋግጣል ። ሁለ ተኛ ቅንጅት ንግድን የማስወገድ ውጤት አለው ። ሶስ ተኛ ሊኖሩ የሚችሉ የቴክኒክ ማሻሻያዎችን የማስገኘት ውጤት አለው፤ ብሎም «የንጹህ» (ማለትም ያልተቀናጁ) ድርጅቶች ከሚያስገኙት በላይ የትርፍ ትርፍ ይሰጣል ። አራተኛ «ከንጹህ» ድርጅቶች አንጻር የተቀናጁትን ድርጅ ቶች አቋም ያጠናክራል ፤ በአስከፊ ውድቀት ወቅት በሚ ደረግ የውድድር ትግል ፤ የጥሬ ዕቃዎች ዋጋ ማሽቆል ቆል ከተመረቱ እቃዎች ወደ ውጤት ዋጋ ማሽቆልቆል ጋር በአንድነት መራመድ ሣይችል ሲቀር የተቀናጁትን ድርጅቶች ያጠናክራቸዋል ።[3] »

በተለይ በጀርመን የብረት ኢንዱስትሪ ስለ « ተደ ባለቁት » ማለትም ስለተቀናጁት ድርጅቶች አንድ መጽ ሐፍ የጻፈው ፤ የጀርመኑ ቡርዧ ኤኮኖሚስት ፤ ሄይማን እንዲህ ይላል ፤ «ንጹህን ድርጅቶች ዳብዛቸው ይጠፋል፤ በዝቅተኛ ዋጋ ለገበያ በቀረቡ ምርቶችና በከፍተኛ ዋጋ ጥሬ እቃዎች መካከል ይገጫሉ ። « ስለሆነም የሚከተ ለውን ሥዕል እናገኛለን ፤ » በአንድ በኩል ፤ በዓመት ሚሊዮን ቶን የሚያመርቱት ፤ በከሰል ሲንዲኬታቸው

/በጋራ ፍላጐት ላይ የተመሠረተ የንግድ ድርጅት ተቋም/ ተጠናከረው የተቋቋሙ ትልልቅ የከሰል ኩባንያዎችና በሌላ በኩል የራሳቸው የአረብ ብረት ሲንዴኬት ኖሯቸው ከከሰል ማዕድናት በቅርብ የተጐዳኙ ትልልቅ የአረብ ብረት ድርጅቶች ይቀራሉ ። እነዚህ ከከፍተኛ ንጥረ ነገር፤ከሰል ውጤትና ወደ አለቀላቸው የአረብ ብረት ዕቃዎች ጋር በዓመት 400,000 ቶንስ የአረብ ብረት የሚያመርቱ ፤ በኩባንያው ቤቶች የሚኖሩ አንዳንድ ጊዜም የራሳቸው የባቡር መስመሮችና ወደቦች ያሏቸው ፣ አስር ሺህ ሠራተኞችን የሚቀጥሩ ፤ ግዙፍ ድርጅቶች፤የጀርመን ብረትና የአረብ ብረት ኢንዱስትሪ ዓይነተኛ ወኪሎች ናቸው ። ክምችትም እየቀጠለ ይሄዳል ። ተናጠል ድርጅቶችም እያደጉ ይሄዳሉ ። በአንድ ወይንም በአያሌ የተለያዩ ኢንዱስትሪዎች ውስጥ ቁጥራቸው ምን ጊዜም እየጨመረ የሚሄዱት ድርጅቶች ግማሽ ደርዘን በሚሆኑ ትልልቅ የጀርመን ባንኮች እየተደገፉና እየተመሩ በግዙፍ ድርጅቶች ይጠቃለሉ ። የጀርመንን የማዕድን ኢንዱስትሪ በሚመለከት ፤ ስለ ክምችት ትምህርቶች ካርል ማርክስ የሰነዘረው ሀቅ በትክክል ተረጋግጧል ። ይህ የሚሠራው አንድ ኢንዱስትሪ በታሪፎችና በጭነት ተመኖች ከለላ ሥር በሚሆንበት ሀገር ነው ። የጀርመን የማዕድን ኢንዱስትሪ ለብዝበዛ የበሰለ ነው ።[4] »

አንድ በአጋጣሚ ቅን የሆነ የቡርዧ ኤኮኖሚስት ሊደርስበት የሚገባ መደምደሚያ ይህ ነው ። ኢንዱስትዎቿ በከፍተኛ ታሪፎች ከለላ ሥር በመሆናቸው ፤ ጀርመንን በአንድ በተለየ ክፍል የተመደበች አስመስሎ ማቅረቡ መታወስ አለበት ። ይሁን እንጂ ይህ አጋጣሚ ክምችትንና የሞኖፖሊስት አምራቾችን ማኅበሮች ፤ የካርቴሎችን ፤ የሲንዲኪቶችን ወ ዘ. ተ. መመስ

ረት ብቻ ነው የበለጠ የሚያፋጥነው ። ነጻ የንግድ ልውውጥ ባለበት በእንግሊዝ ፤ ዘግየት ካለ በኋላና ምናልባትም ለየት ባለ ቅርጽም ቢሆን እንኳን ከምችት ወደ ሞኖፖሊ እንደሚያመራ ማስታወሱ እጅግ በጣም ጠቃሚ ነው ። ፕሮፌሰር ኸርማን ሌቪ በእንግሊዝ የምጣኔ-ሀብት ዕድገት ማስረጃዎች ላይ ተመስርቶ - የሞኖፖሊዎች ካርቴሎችና ትረስቶች በሚል ርዕስ ባቀረበው ልዩ ምርምር ውስጥ እንዲህ ይላል ።

« በታላቋ ብሪታንያ ፤ የሞኖፖሊስት አዝማሚያን አቅፎ የሚይዘው ፡ የድርጅቶች መጠንና የሱ ከፍተኛ የቴክኒክ ደረጃ ነው ። ይህ የሚሆነው በአንድ ወገን ፤ ለአዲስ ድርጅቶች አዲስ ወረት የማስፈለጉን ጥያቄ ለሚአመጣውና ከዚያም ዘመቻቸውን ይበልጥ ለችግር ለሚዳርገው በእያንዳንዱ ድርጅት ከፍተኛ የወረት መዋዕለንዋይ ስለሚውልበት ነው ። ከዚህም በላይ /ይህም ለኛ በጣም ጠቃሚ ነጥብ ይመስለናል / ከርሱ ቀደም ብለው በክምችት ከተመሠረቱ ግዙፍ ድርጅቶች ጋር በአንድነት ለመራመድ የሚፈልግ እያንዳንዱ አዲስ ድርጅት ፤ እዚህ ላይ ተጠያቂነት ከመጠን በላይ በመጨመሩ ምክንያት በትርፍ በመሸጥ ሊያጣራቸው የሚችላቸውን ከፍተኛ መጠን ያላቸው ትርፍርፍ ዕቃዎችን ያመርታል፤በስተቀር ይህ ትርፍርፍ ለአዲሱ ድርጅት ሆነ ለሞኖፖሊ ቅንጅቶች ትርፍ በማያስገኝ አኳኋን ተመኖችን እንዲወርዱ ያስገድዳል ። » የከለላ ታሪፎች የካርቴሎችን መመሥረት ከሚአጠናክሩት ሌሎች ሀገሮች እንግሊዝ የምትለየው ፤ የሞኖፖሊስት አፈብራኪ ማኅበሮች ፤ የካርቴሎችና የትረስቶች አብዛኛውን የሚመጣበት ምክንያት ፡ የዋና ተወዳዳሪ ድርጅቶች ቁጥር ወደ « ሁለት ደርዘን ወይንም ወደዚያው ገደማ » ሲወርዱ ከመሆኑ ላይ ነው ።

«እዚህ በመላው የኢንዱስትሪ መስክ፤ በትልልቅ የኢን ዱስትሪ ሞኖፖሊዎች መሠረት ላይ የክምችት ተጽዕኖ ስሜት ቁልጭ ብሎ ጐልቶ ይታያል ።[5] »

ከግማሽ ምዕተ ዓመት በፊት ማርክስ ካፒታልን እየጻፈ በነበረበት ጊዜ ለአያሌ ኤኮኖሚስቶች ነጻ ውድድር እንደ « ተፈጥሮ ሕግ » ሆኖ ታይቷቸው ነበር ። ይሩ ማይ ንስ በንድፈ—ሃሣባዊና ታሪካዊ የካፒታሊዝም ትንታኔ፤ ነጻ ውድድር የምርት ክምችትን ማስከተሉ ይህም በተ ራው ፤ በአንድ የዕድገት ደረጃ ወደ ሞኖፖሊ ማምራቱን ያረጋገጠውን ማርክስ ያቀረባቸውን ጽሑፎች ለመግደል በዝምተኝነት ሴራ ሙከራ አድርጎ ነበር ። ዛሬ ሞኖፖሊ ሀቅ ሆኗል ። ኤኮኖሚስቶች ሞኖፖሊ የተገለጠባቸውን ልዩ ልዩ ሁኔታዎች ያብራሩባቸውንና በአንድነት «ማር ክሲዝም ውድቅ ሆነ » እያሉ የለፈፉባቸውን የመጽሐ ፍት ክምር እያቀረቡ ናቸው ። ይሁን እንጂ ፤ ሀቆች ግትር ነገሮች ናቸውና እንግሊዞች እንደሚተርቱት ወደድንም ጠላንም ግምት ውስጥ ልናስገባቸው ይገባል ። ሀቆቹ የሚያሣዩት ፤ በካፒታሊስት ሀገሮች መካከል ያሉት ልዩ ነቶች ፤ ለምሣሌ ከለላን ወይንም ነጻ ንግድን አስመልክቶ፤ እዚህ ግባ የማይባለውን የሞኖፖሊዎችን ቅርጽ ወይንም የታዩበትን ጊዜ ነው የሚያመለክቱት ። በተጨማሪም ሀቆቹ የሚያሣዩት በምርት ክምችት ምክንያት የሞኖፖሊዎች መፈጠር የካፒታሊዝም የአሁኑን የዕድገት ደረጃ አጠቃ ላይና መሠረታዊ ሕግ መሆኑን ነው ።

ለአውሮፓ ፤ አዲሱ ካፒታሊዝም የቀድሞውን የተ ካበት ጊዜ ፤ ተቀባይነት ባለው ትክክለኛነት በእርግጥ ሊቀርብ ይችላል ፤ የሃያኛው ምዕተ ዓመት መግቢያ ነበር። በቅርቡ ከተጠናቀሩት « የሞኖፖሊ አመሠራረት » ታሪክ ጽሑፎች በአንደኛው ውስጥ የሚከተለውን እናገኛለን ፤

« ስለ ካፒታሊስት ሞኖፖሊ የተነጣጠሉ ምሣሌ ዎችን ፤ ከ1860 ዓ. ም. በፊት ከነበረው ወቅት መጠቃ ቀስ ይቻላል ። በእነዚህ ዛሬ በየቦታው የምናገኛቸውን የቅርጾቹን ፅንስ እንመለከታለን ። ይህ ሁሉ ግን በማያ ጠራጥር ሁኔታ የካርቴሎችን ቅድመ ታሪክ ነው የሚያ መለክተው ። የዘመኑ ሞኖፖሊ ዕውነተኛ መጀመሪያ ጊዜ ፤ በጣም የራቀ እንደሆን ወደ 1860ዎቹ ዓመታት ቢ ሂድ ነው ። የመጀመሪያው የሞኖፖሊ ወሣኝ ወቅት ከሰ ባዎቹ የዓለም አቀፍ የኢንዱስትሪ ዝቅጠት ጀምሮ እስከ ዘጠናዎቹ መግቢያ ድረስ ቆይቷል» ። በአውሮፓውን ደረጃ ጥያቄውን ስንመረምር ፤ የነጻ ውድድር ዕድገት ጣራ የመታው በስድሳዎቹና በሰባዎቹ ውስጥ ሆኖ እና ገኘዋለን ። ከዚህ በኋላ ነው እንግሊዝ የጥንቱን ዓይነት የካፒታሊስት ምሥረታ የፈጸመችው ። በጀርመን ይህ ድርጅት ከእጅ ጥበብ ሥራና ከሀገር ውስጥ ኢንዱስትሪ ጋር የተጧጧፈ ትግል ውስጥ ገባ ፤ እና ለራሱ ሕልውና የሚያስችለውን ቅርጽ ማበጀት ጀመረ ። »

«ታላቁ አብዮት ከ1873ቱ መንኮታኮት ወይንም ደግሞ እሱን ተከትሎ ከመጣውና ይህ ነው የሚባል ማቋረጥ ሣያደርግ በሰማንያዎቹ መግቢያ ላይ የነበረው የዕድገት ዝቅጠት ጋር ጀመረ ፤ እናም ወደ 1889 ዓ. ም. ገደማ የደ ረሰውን ካለወትሮው አመጻዊ ይሁን እንጂ ለአጭር ጊዜ የቆየው ንረት የአውሮፓን ምጣኔ ሀብት ታሪክ ሃያ ሁለት ዓመታት ሂደት ያመለክታል» ። «በ1889 እስከ 90ው የአጭር ጊዜ ንረት ውስጥ የንግድ ሁኔታዎችን ጥሩ አጋ ጣሚ ለመሻማት ሲባል የካርቴልን ሥርዓት በሰፊው መ ማጠን አስፈለገ ። እርኩስ ዓላማ ያለው ፖሊሲ ተመ ኖች በበለጠ ፍጥነት እንዲያድጉና ከካርቴሎች ውጪ ቢሠራ ኖሮ ከሚኖራቸው ተመን ከፍ እንዲሉ ያደርግ

እና ከእነዚህ ካርቴሎች አብዛኞቹ በዚህ ጊዜ አይወድቁ አወዳደቅ ይወድቁ ነበር ። ሌላ የመጥፎ ንግድና የዝቅተኛ ተመን የሃምሳ ዓመት ጊዜ ተከተለ ፤ ሆኖም በኢንዱስትሪ አዲስ መንፈስ ነገሠ ። የዕድገቱ ዝቅጠት መሆን እንዳለ በት ተደርጎ አልተወሰደም ፤ ለሌላ ንረት መግቢያ እን ደተደረገ ዕረፍት እንጂ ።

« የካርቴሉ እንቅስቃሴ ወደ ሁለተኛው ዙር የታ ሪክ ዘመን ተሸጋገረ ። የመሸጋገሪያ ክስተቶች በመሆን ፈንታ ካርቴሎች ከምጣኔ ሀብት ኑሮ መሠረቶች እንደ አንዱ ሆኑ ። እያከታተሉ የኢንዱስትሪውን መስክ በቅ ድሚያም የጥሬ ዕቃዎችን ኢንዱስትሪ በቁጥጥራቸው ሥር አደረጉ ። በዘጠናዎቹ መግቢያ ላይ የካርቴል ሥር ዓት በሱ ቅርጽ የከሰል ሲንዲኬትን ዘግየት ብሎ ለመመ ሥረት ያስቻለውን የኮክ ሲንዲኬት ድርጅት ለማሻሻል በጣም አዳጋች የሆነ የካርቴል ቴክኒክ ይዞ ነበር።ለመጀመ ሪያ ጊዜ፤በአሥራ ዘጠነኛው ምዕተ ዓመት ማለቂያ የደረሰው ከፍተኛንረትና የ1900—3 ቀውስ ሌላው ቢቀር በማዕድንና በብረት ኢንዱስትሪዎች ሙሉ በሙሉ በካርቴሎች ከለላ ሥር ተፈጸመ እና ፤ በወቅቱ እንደ አዲስ ነገር መስሎ ቢታ ይም ፤ አሁን ጠቅላላው ኅብረተሰብ ፤ የምጣኔ—ሀብት ሕይ ወት ሰፋፊ አካባቢዎች ከነጻ ውድድር [6] ግዛት ፤ በአጠቃ ላይ እንደወጣ አድርጎ ነው የሚወስደው ። »

ስለዚህ ፤ በሞኖፖሊዎች ታሪክ ውስጥ ዋና ዋናዎቹ ደረጃዎች የሚከተሉት ናቸው ፤

1. 1860—70 የነጻ ውድድር ዕድገት ከፍተኛ ደረጃ ጣራውን የመታበት ፤ ሞኖፖሊ ምንነቱ ገና ያል ታወቀበት በጽንስነት ደረጃ ላይ ነበር ፤
2. ከ1873ቱ ቀውስ በኋላ ረዘም ያለ የካርቴሎች ዕድገት ወቅት ፤ ሆኖም አሁንም ቢሆን ልዩ

ነበሩ ። ዘላቂ አልነበሩም ። ገና የመሸጋገሪያ ከስተቶች ነበሩ ።

3. በአሥራ ዘጠነኛው ምዕተ ዓመት ማለቂያ ላይ የነበረው ንረት የ1900—3 ቀውስ ካርቴሎች ከመ ላው ምጣኔ—ሀብት ሕይወት መሠረቶች እንደ አንዱ ሆኑ ። ካፒታሊዝም ወደ ኢምፔሪያሊዝም ተሸጋገረ ።

ካርቴሎች ፤ በሽያጭ አከፋፈል፣ወ. ዘ. ተ. ሁኔታ ዎች ላይ ስምምነት ያደርጋሉ ። ገበያዎችን በመካከላቸው ይከፋፈላሉ ። የዕቃዎችን ምርት መጠን ይወስናሉ ። ትር ፎችን በተለያዩ ድርጅቶች መካከል ይከፋፈላሉ፤ወዘተ..።

በጀርመን የነበሩት ካርቴሎች ቁጥር ፥ በ1896 ዓ.ም 250፤በ1905 ዓ ም 385 እንደነበረ ሲገመት ካርቴሎቹ ውስጥ ወደ 12,000 ተቋሞች ተካፋይ ሆነውባቸው ነበር[7]። ይሁን እንጂ በአጠቃላይ እነዚህ አኀዞች የዝቅተኛ ግምት ውጤቶች እንደሆኑ ይታወቃል ። ከላይ ከጠቀስነው የ1907ቱ የጀር መን ስታቲስቲክስ ፤ እነዚህም 12,000 በጣም ታላላቅ ድርጅቶች አገልግሎት ላይ ከዋለው ከግማሽ በላይ የሚ ሆነውን የእንፋሎትና የኤሌክትሪክ ኀይል በአገር ውስጥ እንዳከማቹት ግልጽ ነው ። በተባበሩት አሜሪካ የትረስ ቶቹ ቁጥር በ1900 ዓ. ም. 185 ፥ እና በ1907 250 ተገ ምቶ ነበር ። የአሜሪካ ስታቲስቲኮች ሁሉንም የኢንዱ ስትሪያዊ ድርጅቶች ፀግለሰቦች ይዞታ ሥር ያሉ ፥ በግል ድርጅቶችና በኮርፖሬሺኖች ሥር ያሉ በሚል ይከፋፍ ሏቸዋል ። የመጨረሻዎቹ በ1904 ዓ ም 23.6 እጅ ከመ ቶና በ1909 ዓ. ም. 25.9 እጅ ከመቶ ማለትም በአገሪቱ ውስጥ ካሉት ከጠቅላላው የኢንዱስትሪ ድርጅቶች ከእ

ሩብ በላይ ነበሩ ። እነዚሁ ድርጅቶች በ1904 ዓ. ም. 70.6 እጅ ከመቶ እና በ1909 ዓ. ም. 75.6 እጅ ከመቶ ማለትም ከጠቅላላው ደመወዝተኛ ከሶስት አራተኛ በላይ ሠራተኞች ቀጥረው ነበር ። በዓመት ያመረቱትም ዕሴት ከላይ በተጠቀሱት ሁለት ዓመቶች 10,900,000,00 እና 16,300,000,000 ማለትም ከጠቅላላው 73.7 እና 79 እጅ ከመቶ ነበር ።

ከዚያም ካርቴሎችና ትረስቶች ከጠቅላላው የአንድ የተወሰነ የኢንዱስትሪ ቅርንጫፍ ምርት ሰባት ወይንም ስምንት አሥረኛውን እጅ በግላቸው ያከማቻሉ ። የራይን ዌስትፋሊያን የከሰል ሲንዲኬት በ1893 ዓ ም ሲመሠረት ከጠቅላላው የአካባቢው የከሰል ምርት 86.7 እጅ ከመቶ ያከማቸ ሲሆን በ1910 ዓ. ም. ደግሞ 95.4 እጅ ከመቶ አከማችቷል[8] ። በዚህ መልክ የተፈጠረው ሞኖፖሊ ከፍተኛ ትርፍ ከማረጋገጡም በላይ እጅግ ከፍተኛ መጠን ያላቸውን የቴክኒካዊ አምራች ክፍሎች ወደ መመስረቱ ያመራል ። ዝነኛው ስታንዳርድ የዘይት ኩባንያ በተባበሩት አሜሪካ በ1900 ዓ ም ተቋቋመ ። « በሥልጣን የተፈቀደ የ$150,000,000 ወረት ነበረው ። 100,000,000 የታወቀና የ106,000,000 የዶላር ድብር ለአማራጭነት አሳተመ ፤ ከ1900 ዓ.ም. እስከ 1907 ዓ.ም. ባለው ጊዜ ውስጥ የሚከተለው ድርሻ በ1907 ላይ ተከፍሏል፡48,48,45,44,36,40,40,40 እጅ ከመቶ በተከታታይ ዓመታ ት ተከፍሏል ፤ ማለትም በጠቅላላው 367,000,000 መሆኑ ነው ። ከ1882 እስከ 1907 ከጠቅላላው 889,000,000 ንጹህ ትርፍ ውስጥ 606,000,000 እንደ ድርሻ የተከፋፈለ ሲሆን ፣ ቀሪው ወደ ተቀማጭ ወረት ገቢ ሆኗል[8] ። « በ1907 ዓ. ም የተባበሩት አሜሪካ የአረብ — ብረት ኮርፖሬሽን የተለያዩት የሥራ ዘር

ፎች 210,180 ሠራተኞችን በተጨማሪ ቀጥረው ነበር ። በጀርመን የማዕድን ኢንዱስትሪ ከፍተኛው ድርጅት ፤ ጌልስንኪርቼን የማዕድን ኩባንያ በ1908 ዓ. ም. 46,048 ሠራተኞችና የቢሮ ተቀጣሪዎች ነበሩት[10] ። » በ1902 ዓ.ም የተባበሩት አሜሪካ አረብ ብረት ኮርፖሬሽን 9,000,000 ቶን የአረብ ብረት አምርቶ ነበር[11] ። የምርት ውጤቱ ፤ በተባበሩት አሜሪካ እየተመረተ ከሚወጣው ጠቅላላ የዐረብ ብረት በ1901 ዓ. ም. 66.3 እጅ ከመቶና በ1908 ዓ. ም. 56.1 እጅ ከመቶ ነበር[12] ። የንጥረ ብርቱ የምርት ውጤት በተከታታይ 43.9 እጅ ከመቶና 46.3 እጅ ከመቶ ደርሶ ነበር ።

የአሜሪካ አገዛዝ ኮሚሽን ስለትረስቶች የሰጠው ዘገባ እንዲህ ይላል ፤ « በተወዳዳሪዎቻቸው ላይ የበላይነትን ሊይዙ የቻሉት በድርጅቶቻቸው መጠንና በቴክኒካዊ መሣሪያዎቻቸው ብቁነት ምክንያት ነው ። ከተጀመረ ጀምሮ የትንባሆው ትረስት ጥረቱን ሙሉ በሙሉ የሰውን ሥራ በማሺን በመተካቱ ላይ እንዲያተኩር አድርጎ ነበር ። በዚህ ዓላማ ላይ ተመስርቶ ማናቸውንም ከትምባሆ ምርት ጋር የተያያዙ የመሥራትና የመሸጥ ፈቃዶች በመግዛት ይህ ነው የማይባል የገንዘብ ወጪ አድርጓል ። ለመጀመሪያ ጊዜ ከነዚህ ፈቃዶች አብዛኞዎቹ ጥቅም ስላልሰጡ ትረስቱ በቀጠራቸው መሐንዲሶች አንዳንድ መሻሻል እንዲያደረግባቸው አስፈልጎ ነበር ። በ1906 ዓ. ም. መጨረሻ ላይ ፈቃዶችን ለማግኘት ሲባል ብቻ ሁለት ድጋፍ ሰጭ ኩባንያዎች ተቋቋሙ ። ለተመሣማይ አላማ ፤ ትረስቱ የራሱን የቅርጻ ቅርጽ ማውጫዎች ፤ መጠገኛ ሱቆችን አቋቋሙ ። ከነዚህ ተቋሞች አንዱ ፤ ብሩክሊን ውስጥ ያለው በመካከለኛ ግምት 300 ሠራተኞች ይቀጥራል ። እዚህ የሲጋራን ፤

የሲጋር የሱሬትን ስስ የማሸጊያ ወረቀቶች (እንደሲጋራ ባኮ ብልጭልጭ) ፤ ሣጥኖችን ወ. ዘ. ተ ለማምረት ምር ምር ይደረጋል ። እዚህ በተጨማሪም የምርምር ውጤ ቶች የበለጠ የተሟሉ ይደረጋሉ ።[13] «ሌሎች ትረስቶችም ተግባራቸው አዳዲስ የማምረቻ ዘዴዎችን ማውጣትና የቴክኒክ መሻሻሎችን መፈተን የሆነ የመሻሻል መሐንዲ ሶች የሚባሉ ይቀጥራሉ ። የተባበሩት አሜሪካ የአረብ ብረት ኮርፖሬሽን የቴክኒክ ብቁነትን ከፍ ለማድረግ ወይንም የምርት ወጪውን ለመቀነስ ለሚረዱ አዳዲስ ዘዴዎች ሁሉ ለሠራተኞቹና ለመሐንዲሶቹ ጉርሻ ይሰጣል[14]።»

በጀርመን ከፍተኛ መጠን ያለው ኢንዱስትሪ ለም ሣሌ ባለፉት ጥቂት የአሥር ዓመታት ጊዜ ውስጥ ከመጠን በላይ ባደገው የኬሚካል ኢንዱስትሪ ውስጥ የቴክኒክ መሻሻል ዕድገት በተመሣሣይ መንገድ ይደራጃል። በ1908 ዓ.ም ላይ የምርት ክምችት ሂደት አዝማሚያቸው የሞኖ ፖሊ ይዘት ያለው ሁለት ዋና ዋና « ቡድኖችን » ፈጥ ሯል ። በመጀመሪያ እነዚህ ቡድኖች እያንዳንዳቸው ከሃያ እስከ ሃያ አንድ ማርክ የሚደርስ ወረት ያላቸው የሁለት ትልልቅ ጥንድ ፋብሪካዎች «እጥፍ መጉዳኘት» ይይዛሉ ። በአንድ በኩል ሆሽት ያለው የቀድሞው የሚይስተር ፋብ ሪካና ፍራንክፈርት ያለው የካሲላ ፋብሪካ አሉ ። በሌላ በኩል ሉድዊግሻፌን የሚገኘው የቀለምና የሶዳ ፋብሪካ ፤ እና ኤልበርፌልድ የሚገኘው የቀድሞው የባየር ፋብሪካ አሉ ። ከዚህ በኋላ በ1905 ዓ. ም. ከነዚህ ቡድኖች አንዱ፤ እና በ1908 ዓ. ም ሌላው እያንዳንዳቸው እንደገና ከሌላ ትልቅ ፋብሪካ ጋር ስምምነት አደረጉ ። ውጤቱም ፤ የሁ ለት « ሶስት ጓደኞሞች » እያንዳንዳቸው ከአርባ እስከ ሃምሣ ሚሊዮን ማርክ ወረት ያላቸው መመስረት ነው ።

እነዚህ « ጓደኝነቶች » እየተቀራረቡ ሂደው በተመን ላይ መግባባት ፈጥረዋል[15] ።

ውድድር ወደ ሞኖፖሊ ይለወጣል ። ውጤቱም የም ርት ኅብረተሰብአዊ መሆን ከመጠን በላይ ማደግ ነው ። በተለይም የቴክኒክ ፍልስፍናና መሻሻል ሂደት ኅብረተ ሰብአዊ ይሆናል ።

ይህ ፤ በየቦታው የተበታተኑና የማይገናኙ ፤ ላልታ ወቀ ገበያም የሚያመርቱ የጥንት አፈብራኪዎች ያደር ጉት ከነበረው ውድድር ለየት ያለ ነው ። ክምችት የአን ድን ሀገርና ወደፊት እንደምናየው እንዲያው የብዙ ሀገር ችን ወይንም የመላውን ዓለም ጥሬ ዕቃ ምንጭ / ለምሳሌ የብረት ንጥረ ነገር/ ቀረብ ባለ አኳኋን መገመት የሚያስ ችልበት ደረጃ ድረስ አድጓል ። እነዚህን ግምቶች በማ ድረግ ብቻ ነገሩ መቸ ያበቃና ፤ምንጮቹ በግዙፋንየሞኖ ፖሊ ማኅበሮች ይወረሣሉ እንጂ ። ቀረብ ያለ የገበያዎች የስፋት መጠን ይገመትና ማሕበሮቹ በመካከላቸው በስ ምምነት ይከፋፈሏቸዋል ። የሰለጠነው የሰው ኃይል በሞ ኖፖል ተይዞል ፤ አዋቂ መሐንዲሶች በሥራ ተጠምደ ዋል ፤ መጓጓዣዎች ፤ የባቡር መስመሮች ፤ የአሜሪካ የመ ርከብ ኩባንያዎች በአሜሪካና በአውሮፓ በቁጥጥር ሥር ይውላሉ፤ካፒታሊዝም በኢምፔሪያሊስት ደረጃው በጣም ወደ ተቀነባበረ የምርት ኅብረተሰብአዊ መሆን ያመራል። ካፒታሊስቶቹ ሣይፈቅዱና ፍላጐቱ ሣይኖራቸው ወደ አንድ አዲስ ዓይነት የኅብረተሰብ ቅንጅት ፤ ከሙሉ ነጻ ውድድር ወደ ሙሉ ኅብረተሰብአዊ ማድረግ ጐትቶ ያስ ገባቸዋል ።

ምርት ሕብረተሰባዊ ይሆናል ፤ አወሳሰድ ግን የግል ሆኖ ይቀራል ። የኅብረተሰቡ የምርት መገልገያ የጥቂቶች

የግል ንብረት ሆኖ ይቀራል ። ጥንት ይታወቅ የነበረው የነጻ ውድድር አጠቃላይ መዋቅር እንዳለ ይቆይና የጥቂት ሞኖፖሊስቶች ቀንበር ሊቋቋሙት የማይቻል ይሆናል ።

የጀርመኑ ኤኮኖሚስት ኬስነር በተለይ « በካርቴሎችና ከዚያ ውጪ ባሉት ካፒታሊስቶች መካከል በሚረገው ትግል ላይ » ያተኮረ አንድ መጽሐፍ ጽፏል ። ካፒታሊዝምን በትክክለኛ ገጽታው ለማስቀመጥ ለሞኖፖሊ ማሕበሮች በግዴታ እጅን ስለመስጠት መጻፍ ሲኖርበት ፤ የመጽሐፉን ርዕስ ሣይወዱ መደራጀት ብሎታል ። ሌላው ቢቀር የሞኖፖሊ ማሕበሮች የሚጠቀምባቸውን ዘመናዊ ለድርጅት የሚደረግ የሰለጠነ የትግል ዘዴዎች ዝርዝር መመልከቱ ትምህርት ይሰጣል ።

1. የጥሬ ዕቃዎችን ማቅረብ ማገድ /. . . « ለካርቴሎች አጃቢዎችን ለማፍራት ማስገደጃዎች በጣም ጠቃሚ መንገዶች አንዱ » /
2. አንድ ላይ በማበር የጉልበትን ምንጭ ማገድ (ማለትም በካፒታሊስቶችና በሠራተኛ ማኅበራት መካከል ፤ ማኅበራቱ አባሎቻቸውን ካርቴል በሆኑ ድርጅቶች ብቻ እንዲሠሩ የሚያደርጉ ስምምነቶች)
3. ዕቃ ማቅረብን ማገድ ፤
4. የንግድ በሮችን መዝጋት ፤
5. ከገዢዎች ጋር ንግዳቸውን ከካርቴሎች ጋር ብቻ እንዲያደርጉ ስምምነቶችን ማድረግ ፤
6. ዋጋን በሥነ ሥርዓት መቀነስ(የውጪ ድርጅቶችን ማለትም ለሞኖፖሊስቶች እጃቸውን ለመስጠት ፈቃደኛ ያልሆኑትን ለማጥፋት ዕቃዎችን ለተ

ወሰን ጊዜ ከተመናቸው በታች ለመሸጥ በሚሊ
ዮን የሚቆጠር ገንዘብ ወጪ ይደረጋል ። የቤን
ዚን ዋጋ ከ40 ወደ 22 ማርክ ዝቅ ያለበት ጊዜ
ነበር ፤ ማለትም በግማሽ ያህል)

7. ዱቤን ማገድ ።

8. አድማ ማድረግ ።

እዚህ ላይ በትንሽና በትልቅ ፤ በቴክኒክ ዕድገት ባደ ረጉና ኋላ ቀር በሆኑ ድርጅቶች መካከል የሚደረገውድድር ከእንግዲህ አናይም ። እዚህ ሞኖፖሊስቶች ለነሱ ፈላጭ ቆራጭነት አንገዛም የሚሉትን ጉሮሮዋቸውን ሲያንቁ ነው የምናየው ። ይህ ሂደት በቡርዧ ኤኮኖሚስቶች አእምሮ የሚንጸባረቀው እንደዚህ ነው ።

« በንጹህ የምጣኔ—ሀብት አድማስም እንኳን» ይላል ኬስነር ሲጽፍ «ከንግድ አሠራር ከጥንታዊ የቃሉ አባባል፤ ወደ የወደፊት ጥቅምን በሚያስገኝ የተስፋ ድርጅታዊ አሠ ራር አንድ ዓይነት ለውጥእየተካሄደ ነው ። ከእንግዲህ ዓይነተኛው ድል የሚሄደው የንግድና የቴክኒክ የሥራ ልምድ ኖሮት የገዢውን ፍላጐት የሚያውቅና ለማርካት ለሚችለው ፤ የዕቃዎችን ተፈላጊነት ፈልፍሎ ለማው ጣት ችሎታ ላለው ነጋዴ አይደለም ፤ ግን የወደፊት ጥቅ ሙን ተንትኖ ለማወቅ ለሚችል ብልህ /?!/፤ ግምታዊ አስተያየት መስጠት ወይንም ድርጅታዊ መስፋፋትን አስቀድሞ ለሚያውቅና በድርጅቶችና በባንኮች መካከል አንዳንድ ዝምድና ሊፈጠር መቻሉ ለሚሰማው ነው ።»

ወደ ተራ ሰው ቋንቋ ሲተረጐም ይህም ማለት ምንም እንኳን የሸቀጥ ምርት አሁንም « የነገሠ » ቢሆንምና እንደ ምጣኔ ሀብታዊ ሕይወት መሠረት ሆኖ መታየት

ቢቀጥልም ፤ የካፒታሊዝም ዕድገት ፤ በርግጥም ከተረ ገጠበትና የትርፉ ከፍተኛ ድርሻ ለገንዘባዊ አሠራር « ጠበ ብት » ከሚደርስበት ደረጃ ደርሷል ። ከነዚህ አሠራሮ ችና ማጭበርበሮች ሥር ኅብረተሰብአዊ ምርት አለ ፤ ይሁን እንጂ ይህንን ኅብረተሰብአዊነት ያመጣው ከፍ ተኛ የሰው ልጅ ዕድገት ተስፋ ላላቸው ድርጅቶች አገል ሎት ውሏል ። «በነዚህ መሠረቶች» የካፒታሊስት ኢምፔ ሪያሊዝም አድሃሪ ፤ ንዑስ ከበርቴ ገምጋሚዎች ለ « ነጻ » ሠላማዊ « እና ሐቀኛ » ውድድር እንደሚያልሙ ወደ ኋላ እናያለን ።

« የካርቴሎች መመሥረት ውጤት የሆነው እየተ ራዘመ የናረው ተመን » ይላል ኬስነር « እስካሁን እንደ ታየው በጣም ጠቃሚ የሆኑትን የምርት መገልገያዎችን በተለይም ከሰልን ፤ ብረትንና ፖታሲየንም በሚመለ ከት ነው እንጂ በተፈበረኩ ዕቃዎች ላይ ታይቶም አያ ውቅም ። በተመሣሣይ የተመናች መጨመር ውጤት የሆነው የትርፍ ማደግ ፤ የምርት መገልገያዎችን በሚያ መርቱ ኢንዱስትሪዎች አካባቢ ብቻ ተወስኗል ። በዚህ አመለካከት ላይ ጥሬ ዕቃዎችን የሚያወጡ ኢንዱስት ሪዎች( ከፊል አምራቾችን ሣይጨምር) ወደ ውጤት የተ ለወጡ ዕቃዎችን የሚያመርተውን ኢንዱስትሪ በሚያ ዳክም አኳኋን በከፍተኛ ትርፍ መልክ ሳይሆን ፤ በካርቴ ሎች መመስረት ዕድላቸውን ከማጠናከራቸውም ሌላ በነጻ ውድድር ጊዜ ሊያገኙት የማይችሉትን በሌላ ላይ የበላይ መሆናቸውን የሚያረጋግጡ መሆኑ መታሰብ አለበት[16]።»

መስመር ያሰመርኩባቸው ቃላት ቡርዧ ኤኮኖሚ ስቶች በግዴለሽነትና አልፎ አልፎ አምነው የሚቀበሉ ትን እና በተጨማሪም በካውትስኪ የሚመሩት የዘመኑ የአድርባይነት ተከላካዮች ረቀቅ ባለ መንገድ የሚሸሸጉ

ትንና የሚያገልሉትን ጉዳይ ጽንሰ ሃሣብ ግልጽ ያደርጋሉ ። የበላይነትና ከሱ ጋር የተያያዘው አመጽ ፤ እነዚህ ናቸው ዓይነተኞቹ « የካፒታሊስት ዕድገት የመጨረሻው ዙር » ግንኙነቶች ፤ ከኃይለኛ የምጣኔ ሀብት—ሞኖፖሊዎች መመስረት በኋላ ሊሆን የሚችለው ፤ የሆነውም ፤ የማይቀረው ውጤት ይኸው ነው ።

ካርቴሎች ከሚጠቀሙባቸው ዘዴዎች አንድ ሌላ ምሣሌ አቀርባለሁ ፦— ዋና ዋና የጥሬ ዕቃዎች ምንጮችን በቁጥጥር ሥር ማድረግ ከተቻለ ፤ የካርቴሎች መፈጠርና የሞኖፖሊዎች መመስረት በጣም ቀላል ይሆናል ። ይሁንና የጥሬ ዕቃዎችን ምንጮች መያዝ በማይቻልባቸው ሌሎች ኢንዱስትሪዎች ሞኖፖሊዎች ሊፈጠሩ አይችሉም ብሎ መገመት ስህተት ይሆናል ። የሲሚንቶ ኢንዱስትሪ ለምሣሌ ፤ ጥሬ ዕቃዎችን ከየትም ማግኘት ይችላል ። ሆኖም በጀርመን ይህ ኢንዱስትሪ ከሚገባው በላይ በካርቴል ውስጥ ገብቷል ። የሲሚንቶ አምራቾች የአካባቢ ሲንዴኬት አቋቁመዋል ፤ ደቡብ ጀርመን ፤ ራይን ዌስትፋሊያን ፤ ወ. ዘ. ተ ። የሚተመኑትም ተመኖች የሞኖፖሊ ተመኖች ናቸው ፤ ትክክለኛው ተመን 180 ማርክ ሲሆን ለአንድ መኪና ጭነት ከ230 እስከ 250 ማርክ ይጠየቃል ! ድርጅቶቹ ከ12 እስከ 16 እጅ በመቶ ድርሻን ይከፍላሉ ፤ የዘመኑ ተስፋ ያላቸው ድርጅቶች « ጠበብቶችም » ከወለዱ ሌላ ከፍተኛ ትርፍ ወደ ኪሣቸው እንዴት እንደሚያስገቡ የሚያውቁ መሆናቸው መዘንጋት የለበትም ። የዚህን ዓይነት ትርፍ በሚያስገኝ ኢንዱስትሪ ውስጥ ውድድርን ለማስቀረት ፤ ሞኖፖሊዎቹ የመረባረብ ረቂቅ አሻጥር እስከመጠቀም ይደርሳሉ ፤ በኢንዱስትሪያቸው ላይ ጉዳት የደረሰ በማስመሰል ያወራሉ ፤ ያስወራሉ ፤ ጋዜጦች ... ጸሐፊዎቻቸው ያልታወቁ ማስጠንቀቂያዎች በጋ

ዜጦች ያወጣሉ ፤ የሚከተለው ለምሳሌ ፤ « ካፒታሊስ ቶች ወረታችሁን በሲሚንቶ እንዱስትሪ ውስጥ አታውሉ፤ በመጨረሻም ፤ « የውጪዎቹን »/ ከሲንዴኬት ውጪ ያሉትን/ ከ60,000,እስከ 80,000 እንዲያውም 150,000 ማርክ ድረስ «ካሣ» በመክፈል ይገዟቸዋል[17] ። ሞኖፖሊ፤ ተወዳዳሪዎች «በመካከለኛ» ተመን ከመግዛት እስከ የአሜሪካኑ ዘዴ ፤ በተወዳዳሪዎች ላይ ድማሚት « መጠ ቀም » ድረስ ያለውን የተንኮል ዘዴ እየተጠቀመ መን ገዱን ጥርጊያ ያደርጋል ።

ካርቴሎች ቀውስን ያስወግዳሉ የሚለው አባባል ፤ ካፒታሊዝምን ቀባብተው የሚያቀርቡ የቡርዧ ኤኮና ሚስቶች የሚነዙት ልብ ወለድ ነው ። በተቃራኒው በተ ወሰነ የኢንዱስትሪ ቅርንጫፍ የተመሠረተው ሞኖፖሊ በካፒታሊስት ምርት ውስጥ ባጠቃላይ የውስጥ አካል የሆነውን ሥርዓተ አልባ ያስፋፋል ፤ ያጠናክራል ። የካፒ ታሊዝም ጠባይ የሆነው በእርሻና በኢንዱስትሪ ዕድገት መካከል ያለው አለመስተካከል ይጨምራል ። ከባድ ኢን ዱስትሪ እየተባሉ የሚጠሩት በከፍተኛ ደረጃ ካርቴል የሆኑት በተለይም የከሰልና የብረት አመቺ ሁኔታ ላይ መሆን በሌሎች የኢንዱስትሪ ቅርንጫፎች « አሁንም የበለጠ ያለመግባባት እጥረት» ያስከትላሉ ። «የጀርመንን ትልልቅ ባንኮችና ኢንዱስትሪ ያላቸውን ግንኙነት » በሚ መለከት የቀረበው መጽሐፍ ደራሲ ጂደደልስ እንደሚ ያምነው[18] ።

«አንድ የምጣኔ ሀብት ሥርዓት የበለጠ ባደገ ቁጥር» ይላል ፤ ሀፍረት ቢሱ የካፒታሊዝም ይቅርታ ጠያቂ ሊየ ፍማን ሲጽፍ «የበለጠ ከአደገኛ ድርጅቶች በተጠጋ መጠን ወይንም በሌላ ሀገር ያሉ ድርጅቶች፤ማለትም ለመስፋፋት ረዘም ያለ ጊዜ የሚወስዱ፤ወይንም በመጨረሻ የሀገር ውስጥ

ተጠቃሚነት ባላቸው ለመጠቀም ይገደዳል»[19]፡፡የተጨማመ ረው አደጋ ፤ በረዥሙ ሲታይ ፤ ሞልቶ ትርፍ ወደ ውጪ ሀገር ከሚፈሰው ወ. ዘ. ተ በጣም ብዙ ከሚጨምረው ወረት ጋር ዝምድና አለው ፡፡ በተጨማሪም ከመጠን በላይ በሆነ ፍጥነት የሚያድገው የቴክኒክ እርምጃ በተለያዩ የብ ሔራዊ ምጣኔ—ሀብት መስኮች መካከል መዛባትን ፤ ሥር ዓተ አልባንና ቀውስን ያስከትላል ፡፡ ሊየፍማን ይህንን አምኖ እንዲቀበል ተገዷል ፤ « ምናልባት የሰው ልጅ በቅርቡ የምጣኔ ሀብቱን ሥርዓት የሚለዋወጡ በጣም ጠቃሚ የሆኑ ከፍተኛ የቴክኒክ ለውጦችን ያያል » - -- ኤሌክትሪክሲቲና አቫሲዮን . . . « እንዳጠቃላይ ሕግ ሆኖ በዚህ ቅጽበታዊ የምጣኔ ሀብት ለውጥ ወቅት ፥ በተ ስፋ ላይ ያለው ድርጅት በከፍተኛ ደረጃ ያድጋል[20] ». . . ማናቸውም ዓይነት ቀውሶች ይበልጡን ጊዜ የምጣኔ—ሀብት ቀውሶች እነዚህ ብቻ ባይሆኑም ቅሉ በተራቸው ለጥንካ ሬና ለሞኖፖሊ ያለውን አዝማሚያ በተጠናከረ አኳኋን ያሣድጋሉ ፡፡ ከዚህ ጋር ተያይዞ ከላይ እንደተመለከትነው በዘመናዊ ሞኖፖሊ ታሪክ ውስጥ አቅጣጫ ስላስለወጠው የ1900ው ቀውስ ምክንያት የሚከተለው የጄይደልስ አስ ተያየት ከፍተኛ ትምህርት ያዘለ ነው ፤

«በመጀመሪያ በተመሠረቱት ኢንዱስትሪዎች ውስጥ ከታላላቆቹ ፋብሪካዎች ጋር ጐን ለጐን የ1900 ቀውስ በከፍተኛው የኢንዱስትሪ ንረት ላይ ብቅ ብቅ ያሉ ዛሬ የጥንት ተብለው ሊገመቱ የሚችሉ ፥ « ንጹሐን » (ያል ተቀናጀ) « በፋብሪካዎች መስመር የተደራጁ አያሌ ፋብ ሪካዎች አፍርቷል ፡፡ የተመኖች መውደቅና የዕቃዎች ተፈላጊነት ማዘቅዘቅ ፤እነዚህን «ንጹሐን» ድርጅቶች በከፍተኛ ደረጃ በተቀናጁ ድርጅቶች ላይ ምንም ለውጥ ባላስከተለ ወይንም ለአጭር ጊዜ ለውጥ ባስከተለ ፥ አጠ

ራጣሪ አቋም ላይ አስቀምጧቸው ነበር ። በዚህ ምክንያት የ1900ው ቀውስ ፤ ከ1873ቱ ቀውስ ይልቅ የበለጠ የኢንዱስትሪ ድልበት ፈጥሯል ። የ1873ቱም ደህና ደህና መሣሪያዎች ያላቸው ድርጅቶች እንዲመረጡ አድርጓል ፤ ሆኖም በጊዜው በነበረው ዝቅተኛ የቴክኒክ ዕድገት ምክንያት ይህ ምርጫ ከቀውስ አምልጠው የወጡትን ተቋሞች የሞኖፖሊ አቋም ሊያሲዛቸው አልቻለም ነበር ። የዚህ ዓይነቱ ዘላቂ ሞኖፖሊ በጣም የተወሳሰበ ቴክኒክ ፤ ይህ ነው የማይባል ድርጅትና ወረት ስላላቸው ፤ በግዙፉ ድርጅቶች ፤ በዘመናዊዎቹ የብረትና የዐረብ ብረት እና ኤሌክትሪካል ኢንዱስትሪዎች ውስጥ በከፍተኛ መጠን ሲኖር ፤ በዝቅተኛ መጠን ደግሞ በመሐንዲስ ኢንዱስትሪ ፤ በአንዳንድ የብረታ ብረት ኢንዱስትሪ ቅርንጫፎች ፤ በመጓጓዣ ፤ ወ. ዘ. ተ. ይኖራል[21] » ።

ሞኖፖሊ ! ይህ « የካፒታሊዝም ዕድገት ከፍተኛው ደረጃ » የመጨረሻው ቃል ነው ። ይሁን እንጂ ፤ ባንኮች የሚጫወቱትን ክፍል ካልገመገምን ስለዘመኑ ሞኖፖሊ ምንነትና እውነተኛው ኃይሉ ብቂ ያልሆነ ፤ያልተሟላ እና ደካማ አመለካከት ነው የሚኖረን ።

ምዕራፍ ሁለት

# ባንኮችና አዲሱ ሚናቸው

ዋነኛውና የመጀመሪያው የባንኮች ተግባር ፤ ክፍያዎችን ለማከናወን ፤ እንደ አገናኝ ማገልገል ነበር ። ይህንም በማድረጋቸው የማይንቀሳቀሰውን የጥሬ ገንዘብ ወረት እንዲንቀሳቀስ ፤ ያደርጋሉ ፤ ማለትም ትርፍ ወደ

ሚያስገኝ ወረት ይሳውጣሉ ፤ ማናቸውንም ዓይነት የገን ዘብ ገቢ በመሰብሰብ ለካፒታሊስቱ መደብ አገልግሎት ሥራ እንዲውል ያደርጋሉ ።

የባንክ ሥራ እየተስፋፋና በጥቂት ድርጅቶች ውስጥ እየተከማቸ ሲሄድ ፤ ባንኮች ከጥምት አገናኝነት የመላ ካፒታሊስቶችንና ትንንሽ ነጋዴዎችን የጥሬ ገንዘብ ወረ ትና ፤ በአንድ ሃገርና በሌሎችም ሃገሮች ውስጥ የምርት መገልገያዎችን ከፍተኛውን እጅ የጥሬ ዕቃዎች ምንጮ ችን ፤ በቁጥጥራቸው ሥር ወደሚያደርጉ እፍኝ የማይ ሞሉ ሞኖፖሊስቶች መለወጥ ፤ በካፒታሊዝም ወደ ካፒ ታሊስት ኢምፔሪያሊዝም ዕድገት ውስጥ ካሉት መሠረታ ውያን ሂደቶች አንዱን ያመለክታል ። ስለሆነም ፤ ከሁሉ አስቀድመን የባንክ ሥራ ክምችትን እንመረምራለን ።

በ1907 — 08 ፤ እያንዳንዳቸው በሚሊዮን ማርክ የሚገመት ወረት የነበራቸው የጀርመን ውሁድ ድብል ባንኮች (ጆይንት ስቶክ ባንኮች) ፤ ያጠራቀሙት ገንዘብ ሲደመር ወደ 7, 000,000,000 ማርክ ደርሶ ነበር ። በ19 12—13 ይኸው ተቀማጭ ገንዘብ ወደ 9,800,000,000 ማርክ አድጐ ነበር ። በአምስት ዓመት ውስጥ 40 እጅ ከመቶ ጨምሯል ። እና ከጭማሪው 2,800,000,000 ማርክ ውስጥ 2,750,000,000 ማርክ ፤ እያንዳንዳቸው ከ10.000‘000 ማርክ በላይ ካፒታል ለነበራቸው ለ57 ባንኮች ተከፋፈለ ። የተቀማጩ ገንዘብ ለታላላቅና ለታ ናናሽ ባንኮች አከፋፈል እንደሚከተለው ነበር[22] ።

## የተጠራቀመው ገንዘብ ከመቶ ሲታሰብ ፤

| | በ9 የበር ሊን ባንኮች | ከ10ሚ.ማርክ ወረት በላይ ባላቸው በቀሩት 48 ባንኮች | ከ1—10 ሚ. ማርክ ወረት ባላቸው 115 ባንኮች | ከ1ሚ ማርክ በታች ወረት ባላቸው ትንንሽ ባንኮች |
|---|---|---|---|---|
| 1907—08 | 47 | 32.5 | 16.5 | 4.0 |
| 1912—13 | 49 | 36.0 | 12.0 | 3.0 |

ከጠቅላላው ተቀማጭ ወደ ግማሽ የሚሆነው ባለቤት የሆኑ ዘጠኝ ባንኮች ያሉባቸው ትልልቅ ባንኮች ፣ ትንንሾቹን ባንኮች እየዋጧቸው ነው ።

ነገር ግን ፤ ብዙ ጥቃቅን ነገሮችን ለምሳሌ የብዙ ትንንሽ ባንኮች ወደ ትልልቅ ባንኮች ቅርንጫፎችነት በትክክል መለወጥን ፤ ወዘተ . . . ሳንጠቅስ አልፈናል ። ስለዚህ ወደኋላ ላይ እናወሳዋለን ።

በ1913 ዓ. ም. መጨረሻ ላይ ወደ 10,000,000,000 ማርክ ከሚጠጋ ጠቅላላ ተቀማጭ ውስጥ ፤ ዘጠኙ የበርሊን ባንኮች ወደ 5,100,000,000 ማርክ ተቀማጭ እንደ ነበራቸው ሹሊዝ ጋቨርኒትዝ ገምቶ ነበር ። ተቀማጮችን ብቻ ሣይሆን ፤ ጠቅላላውን የባንክ ወረት በማስመልከት ደራሲው ሲጽፍ ፤ « በ1909 ዓ. ም. መጨረሻ ላይ ፤ ዘጠኙ ትልልቅ የበርሊን ባንኮች ከተዛመዷቸው ባንኮች ጋር ፤ 113,000,000,000 ማርክ ማለትም ከጠቅላላው የጀርመን ባንክ ወረት ወደ 83 እጅ በመቶ የሚሆነውን ይቆጣጠሩ ነበር ።

ከተዛመዱት ባንኮች ጋር በአንድነት 3,000,000,000 ማርክ ይቆጣጠር የነበረው የዳች ባንክ ፤ ከፕሩሲያን የባቡር አስተዳደር ጋር ጐን ለጐን በዓለም ላይ ትልቁንና በጣም ማዕከላዊ — ቢስ የሆነውን የካፒታል ክምችት ይወክላል ።[23] »

« የተዛመዱ » ባንኮች የሚለው ማገናዘቢያ ላይ አጽንኦት ያደረግሁት የዘመናዊው ካፒታሊስት ክምችት በጣም ጠቃሚ መለያ ባህሪይ እሱ በመሆኑ ነው ። ትልልቅ ተቋሞችና በተለይም ባንኮች ፤ ትንንሾቹን ሙሉ በሙሉ መዋጥም ብቻ ሣይሆን ፤ « ያቀላቅሏቸዋል » ፤ ይሚኑአቸዋል ፤ አክስዮኖችን በመግዛት ወይንም በመለወጥ በዱቤ አሠራር በመጠቀም በወረታቸው ውስጥ « ይዞታታውን » በመውሰድ ወደ ፡ « ራሳቸው » የኮንሰርን ድርጅት (ቴክኒካዊ ቃሉን ለመጠቀም) ይስቧቸዋል ። ስለ ዘመናዊው « መያዣና ፊናንስ ኩባንያዎች » በመግለጽ ፥ ፕሮፌሰር ሊየፍማን ወደ 500 ገጾች ያሉት አንድ ትልቅ « መጽሐፍ » ጽፏል[24] ። የሚያሳዝነው ፤ በጣም ደካማ የሆኑ ፤ ያልተዛመዱ ሀሣቦች ተደጋግሞ የተጠቀሰባቸው « ንድፈ-ሃሣባዊ » ነጸብራቆች መጽሐፉ ውስጥ ታክለውበታል ። ይህ « የይዞታ » ሥርዓት ፤ ክምችትን በሚመለከት ምን ውጤት እንደሚያስከትል ፤ ስለ ትልልቅ የጀርመን ባንኮች እሱ ራሱ የባንክ ሠራተኛ የሆነው ሪየዘር በጻፈው መጽሐፍ ውስጥ በሚገባ ተብራርቷል ። ይሁንና የሱን መረጃ ከመርመራችን አስቀድሞ ፤ ስለ « ይዞታ » ሥርዓት ፤ አንድ ተጨባጭ ምሳሌ እንጥቀስ ።

የጀርመን ባንክ « ቡድን ፤ » የመጨረሻው ትልቁ ባንክ ባይሆንም ከትልልቆቹ ባንኮች አንደኛው ነው ። በዚህ ቡድን ውስጥ ፤ ባንኮቹን ያስተሣሠሯቸውን ዋና ነገሮች ለመጠቆም ፤ በአንደኛ፤በሁለተኛና በሶስተኛ «የይ

ዞታ » ደረጃዎች መካከል ለይቶን ማየት ፤ ወይንም የዚሁ ተመሣሣይ ፤ በአንደኛ፤ በሁለተኛና በሶስተኛ የጥገኝነት (የትንንሾቹ ባንኮች በጀርመን ባንክ ላይ ) ደረጃ መካከል መለየት ይኖርብናል ። ከዚህ በኋላ የሚከተለውን ዝር ዝር እናገኛለን [25] ።

| | 1ኛ ደረጃ ጥገኝነት | 2ኛ ደረጃ ጥገኝነት | 3ኛ ደረጃ ጥገኝነት |
|---|---|---|---|
| የጀርመን ባንክ ይዞታ አለው | በቋሚነት በ17 ባንኮች ውስጥ | ከ34 በ9 ውስጥ | ከ7 በ4 ውስጥ |
| | ላልተወሰነ ጊዜ በ5 ,, ,, | ==== | ==== |
| | አልፎ አልፎ በ8 ,, ,, | ከ14 በ5 ውስጥ | ከ2 በ2 ውስጥ |
| | ድምር በ30 ,, ,, | ከ48 በ14 ውስጥ | ከ9 በ6 ውሰጥ |

በዳች ባንክ ላይ ጥገኛ ከሆኑት «በመጀመሪያ ደረጃ» «አልፎ አልፎ ባሉት» 8 ባንኮች ውስጥ ሶስት የውጪ ሃገር ባንኮች ፤ አንድ የአውስትሪያ (ቬነር ባንክሽሬን) እና ሁለት የሩሲያ (የሳይቤርያ ንግድ ባንክና የሩስያ የውጭ ንግድባንክ) አሉበት ። በጠቅላላው የጀርመን ባንክ በቀጥታናበተዘዋ ዋሪ በከፊልና ሙሉ በሙሉ 87 ባንኮችን ያጠቃልላል ፣ እናም ጠቅላላው ወረት የራሱና እሱ የሚቆጣጠራቸው ሌሎች በሁለትና በሶስት ቢሊዮን ማርክ መካከል ይሆናል ተብሎ ይገመታል ።

ለእንደዚህ ዓይነቱ ቡድን በበላይነት የሚቆምና እንደ የመንግሥት ብድር ማሣለፍ ለመሣሰሉ በተለይ ትርፍ የሚያስገኙ ገንዘባዊ ስራዎች ለመሥራት ሲል በመ ጠን ከሱ አነስ ከሚሉ ጥቂት ባንኮች ጋር ስምምነት ውስጥ የሚገባ አንድ ባንክ «የአገናኝነት» ክፍልን አልፎ አድጐ እፍኝ የሚሆኑ ሞኖፖሊዎች ጭምር መሆኑ ግልጽ ነው ።

በአሥራ ዘጠነኛው ምዕተ ዓመት ማለቂያና የሃያኛው ምዕተ ዓመት መግቢያ ላይ በጀርመን የባንክ ሥራ ክም ችት ያደገበትን ፍጥነት ከሬይዘር በማህጸረ ቃል መልክ ከጠቀስነው ቀጥሎ ከተሰጠው መረጃ ማየት ይቻላል ።

## ስድስት ትልልቅ የበርሊን ባንኮች

| ዓመት | በጀርመን ያሉ ባንኮች | የማስቀመጫ ባንኮችና የምን ዛሪ ቢሮዎች | የማያቋርጥ ይዞታ በጀር መን ውሁድ ድብል ባንኮች | ጠቅላላ ተቋሞች |
|---|---|---|---|---|
| 1895 ——— | 16 | 14 | 1 | 42 |
| 1900 ——— | 21 | 40 | 8 | 80 |
| 1911 ——— | 104 | 276 | 63 | 450 |

መላውን ሃገር የሚሸፍን ጠቅላላውን ወረት የዓመት ገቢ ወደ መካከል የሚበሰብስ ፤ በብዙ ሺህ የሚቆጠሩ የተበታተኑ ድርጅቶችን ወደ አንድ ብሔራዊ ካፒታሊ ስት ብሎም አለም አቀፍ ካፒታሊስት ምጣኔ ሀብት የሚ ለውጥ ፤ የአንድ የቦደዎች መረብ በፍጥነት መስፋፋት እናያለን ።

ሹልዝ ጋቨርኒትዝ ከዚህ በፊት በጠቀስነው ጽሑፍ ውስጥ እንደ የዘመኑ ቡርዧ ፖለቲካዊ ኤኮኖሚ ተንታኝ የሚናገርለት ፤ « ማዕከላዊ ቢስ » (ዲሴንትራላይዜሽን) ቀድሞ በአንጻራዊ አነጋገር « ጥገኛ ያልሆኑ ፤ » ቁጥራ ቸው እየጨመረ የሚሔድ ወይንም የሀገር ውስጥ ምጣኔ-ሀብት አካሎች ለአንድ ማዕከላዊ አካል በትክክል ተገዥ መሆን ማለት ነው ። እንደ እውነቱ ከሆነ ማዕከላዊነት ነው የሞኖፖሊስት ኃያላን ሚና ፤ ጥቅምና ሥልጣን የሚ ያጠናክረው ።

በቀድሞ ካፒታሊስት አገሮች ይህ « የባንክ ሥራ መረብ » የበለጠ የተቀራረበ ነው ። በታላቋ ብሪታንያና በአየርላንድ በ1910 ዓ. ም. በጠቅላላው 7151 የባንክ ቅርንጫፎች ነበሩ ። አራት ትልልቅ ባንኮች እያንዳንዳ ቸው ከ400 በላይ ቅርንጫፎች /ከ447—689/ ነበሯቸው። አራቱ ከ200 በላይ ቅርንጫፎች እያንዳንዳቸው ፤ አሥራ አንዱ እያንዳንዳቸው ከ100 በላይ ቅርንጫፎች ነበሯቸው ።

በፈረንሣይ ሶስት ትልልቅ ባንኮች ፤ ክሬዱት ሊዮኒስ ፤ ኮምቶር ናሽናልና ፣ ሶሲየቴ ዠኔራል ሥራቸውንና የቅርንጫፎች መረባቸውን በሚከተለው አኳኋን አስፋፍተው ነበር[26] ።

የቅርንጫፎችና የቢሮዎች ቁጥር ወረት በሚሊዮን ፍራንክ

| | በክፍለ ሀገራት | በፓሪስ | ጠቅላላ | የራስ ወረት | የብድር ወረት |
|---|---|---|---|---|---|
| 1870 | 47 | 17 | 64 | 200 | 427 |
| 1890 | 192 | 66 | 258 | 265 | 1245 |
| 1909 | 1033 | 196 | 1229 | 887 | 4363 |

የአንድን ትልቅ ዘመናዊ ባንክ «ግንኙነቶች» ለማሣየት በጀርመንና በዓለም ካሉት ትልልቅ ባንኮች አንዱ የሆነው ዲስኮንቶ ጌሴልሻፍት/ ያለው ወረት በ1914 300 ሚሊዮን ማርክ ነበር/ ያደረጋቸውን የደብዳቤዎች መላክና መቀበል ዝርዝር ከዚህ ቀጥሎ እናቀርባለን ።

| | የደረሱት ደብዳቤዎች | የተላኩት ደብዳቤዎች |
|---|---|---|
| 1852 | 6135 | 6292 |
| 1870 | 85,800 | 87,513 |
| 1900 | 533,102 | 626043 |

የትልቁ የፓሪስ ባንክ የክሬዲት ሊዮኒ የደምበኞች ብዛት በ1875 ዓ. ም ከነበረው 28535 ወደ 633,539 በ19 12 ዓ. ም. ከፍ ብሏል [27] ።

የወረት መድሉብና የባንክ በንግድ ሥራ ውስጥ የሚሠራቦት የሺያጭ ታክስ ዕድገት ምን ያህል የባንክን ዓይነትኛነት በአጠቃላይ እንደሚለዋውጡት ፤ ከረዥም በሥርአት የቀረቡ ሐተታዎች ይልቅ ፤ በተሻለ መንገድ እነዚህ ደምበኛ አሀዞች ያብራራሉ ። የተበታተኑ ካፒ ታሊስቶች ወደ አንድ የሕብረት ካፒታሊስትነት ያለወ ጣሉ ። የጥቂት ካፒታሊስቶችን ተንቀሳቃሽ ገንዘብ በሚ ያዘጋጅበት ጊዜ ፤ ባንኮች እንደ ደንቡ ቴክኒካዊና በተለይ ረዳት ተግባሮችን ብቻ ያከናውናሉ ። ይህ ሥራ እጅግ ከፍ ተኛ በሆነ መጠን በሚያድግበት ጊዜ ግን እፍኝ የማይሞሉ ሞኖፖሊስቶች የጠቅላላውን የካፒታሊስት ሕብረተሰብ የንግድና የኢንዱስትሪ ሥራዎች ለነሱ ፈቃድ እንዲገዙ ሲያደርጉ እናገኛቸዋለን ፤ ምክንያቱም በመጀመሪያ ደረጃ፤ የብዙዎችን ካፒታሊስቶች ገንዘብዊ አቋም በትክክል ለማረጋገጥ ፤ ከዚያ በኋላ ሊቆጣጠሯቸው ፤ ለዱቤዎች በሩን ለማጥበብ ወይንም ለማስፋት ፤ ዱቤዎችን ለመፍ ቀድ ፤ ወይንም ለመከልከል እና በመጨረሻም የወደፊት ዕድላቸውን በጠቅላላ ገቢያቸውን ለመወሰን ፤ ወረት ሊያሣጧቸው ወይንም ወረታቸው በፍጥነት በከፍተኛ መጠን እንዲያሣድጉ ሊያደርጉላቸው ፤ ወ. ዘ. ተ ዕድል ስለሚያገኙ ነው ።

ጥቂት ከፍ ብለን የበርሊኑን የዲስከንቶ ጌሴልሻፍት 300,000,000 ማርክ ወረት ጠቅሰን ነበር ። ይህ የባንኩ ወረት ዕድገት በሁለቱ ታላላቅ የበርሊን ባንኮች ጀርመን ባንክ እና ዲስኮንቶ መካከል ለበላይነት ለተደረገው ትግል

ከመንግሥኤዎቹ አንዱ ነበር።በ1870 ዓ.ም. የ15,000,000 ማርክ ወረት የነበረው የመጀመሪያው ሲሆን ሁለተኛው ግን 30,000,000 ማርክ ወረት ነበረው ። በ1908 ዓ.ም. የመጀመሪያው 200,000,000 ማርክ ወረት ሲኖረው ሁለተኛው 170,000,000 ማርክ ወረት ነበረው ። በ1914 ዓ. ም የመጀመሪያው ወረቱን ወደ 250,000,000 ማርክ ከፍ ሲያደርግ ሁለተኛው ከሌላ የአንደኛ ደረጃ ባንክ ከሻፍሀውንሼር ባንክሽሬን ጋር በመዋሃድ ወረቱን ወደ300000 000 ማርክ አሳደገ ። እርግጥም ከዚህ ለበላይነት ከሚደረገው ትግል ጋር ጐን ለጐን ሥራ ላይ የሚውሉበት ጊዜ እየጨመረ የሚሄድ በየጊዜው በሁለት ባንኮች መካከል « ስምምነቶች » ይደረጉ ነበር ። የሚከተሉት ውሣኔዎች ፤ ይህ የባንክ ሥራ ያደረገው ዕድገት የምጣኔ-ሀብት ጥያቄዎችን በጣም መካከለኛና ጥንቃቄ የተሞላበት የቡርዧ ጠጋኝነትን ድንበር ከማይዘሏ አቅጣጫ የሚመለከቱትን የባንክ ጠበብት ፤ የሚያስገድዱበት ናቸው።

ዲስኮንቶ ጊሲልሻፍት ባደረገው የ300 000 000 ማርክ የወረት ዕድገት ላይ ዳይባንክ የተባለው የጀርመን መጽሔት ሪቪው ሲተች ፤ ሌሎችም ባንኮች ይህንኑ ፈለግ ስለሚከተሉ ፤ ከጊዜ በኋላ ዛሬ ጀርመንና በምጣኔ፤ሀብት መልክ የሚያስተዳድሯት ሶስት መቶ ሰዎች ቀስ በቀስ ወደ ሃምሣ ፤ ሃያ አምስት ፤ ወይንም ከዚ.የም ወዳነስ ቁጥር ሊቀነሱ ይችላሉ ። ከቅርብ ጊዜ ወዲህ ፤ ይህ ለማድለብ የሚደረገው እንቅስቃሴ በባንክ ሥራ ብቻ ይወሠናል ተብሎ አይጠበቅም ። በያንዳንዶቹ ባንኮች መካከል ያለው የቀረበ ዝምድና እነዚህ ባንኮች የሚያቀርቧቸውን የኢንዱስትሪ ሲንዲኬቶች ወደማቀራረቡ ያመራል።

በአንድ ብሩህ ጠዋት ትረስቶችን እንጂ ሌላ ነገር ባለማየት ለመደነቅ እንነቃ ይሆናል ፤ እና የግል ሞኖፖ

ሊዎችን ወደ መንግሥት ሞኖፖሊዎች የመለወጡን አስ ፈላጊነት ፊት ለፊት እንጋፈጣለን ። ይሁን እንጂ ነገሮች የራሳቸውን የዕድገት መሥመር ፤ በመድበሎች አንቀሣ ቃሽነት ፍጥነታቸውን እየጨመሩ ፤ ተከትለው እንዲ ጓዙ ከመፍቀዳችን በስተቀር በሌላ በምንም ራሣችንን ልንወቅስ አንችልም[28] ።

የቡርዧ ሣይንስ ሙሉ በሙሉ ሐቀኛ ባለመሆኑና የነገሩን ጽንሰ ሃሣብ ማጨለም ዛሬን በቁጥጥሮ ለመ ከለል ጥረት በማድረጉ ከሱ የቡርዧ ጋዜጠኛነት ሙት ነት ይህ ጥሩ ምሳሌ ነው ። በመድለብ ውጤቶች«መደነቅ» የካፒታሊስት ጀርመንን ወይንም የካፒታሊስት « ህብ ረተሰብን » (እኛን ራሣችንን) አስተዳደር « መንቀፍ » መድበሎችንና አክሲዮኖችን ሥራ ላይ እንዲውሉ ማድ ረግ ፤ ልክ የጀርመኑ « ካርቴል » ባለሙያ ትሺየርሲኪ ፤ የአሜሪካንን ትረስቶች እንደፈራውና የጀርመንን ካር ቴሎች እንደ ትረስቶቹ ቴክኒካዊውና ምጣኔ-ሀብታዊ ዕድገት ከመጠን በላይ ላያፈጥኑ ይችሉ ይሆናል በሚል ምክንያት « እንደመረጠው ፥ » መድለብን « ያፋጥናሉ » ብሎ መፍራት ፥ ይህ ሙትነት አይደለምን[29] ?

ይሁን እንጂ ሀቆች በሀቅነታቸው ይቆማሉ ፤ በጀ ርመን ትረስቶች የሉም ፤ ካርቴሎች «ብቻ» እንጂ ። ነገር ግን ጀርመን ከሶስት መቶ በማይበልጡ የወረት ማሕበሮች ነው የምትተዳደረው ። የነዚህም ቁጥር በየጊዜው እየቀ ነሰ ነው ። በማናቸውም ሁኔታ በሁሉም የካፒታሊስት ሃገሮች የባንክ ሥራ ህግጋት ቢለያዩም ባንኮች የወረትን ክምችት ሂደትና የሞኖፖሊዎችን መመሥረት በከፍተኛ ደረጃ ያባብሣሉ ፥ ያፋጥናሉ ።

የባንክ ሥራ ሥርአት « በርግጥ የማንኛቸውንም መዝገብ አያያዝና በሕብረተሰብ ደረጃ የምርት መግለገ

ያዎች ሥርጭት ቅርጽ ያቀርባል፤ ነገር ግን ሲያቀርብ ቅር ጹን ብቻ ነው ። »ይላል ማርክስ ከግማሽ ምዕተ ዓመት በፊት በካፒታል ውስጥ ሲጽፍ (የሩሲያ ትርጉም ፤ ቅጽ 3 ክፍል ሁለት ፥ ገጽ 144) ። ስለባንክ ወረት ዕድገት ፤ ስለ ታላላቅ ባንኮች ፤ ቢሮዎችና ቅርንጫፎች ቁጥር መጨ መር ፤ ስለየአካውንታቸው ቁጥር ማደግ፣ ወ. ዘ.ተ ጠቅ ሰናቸው የነበሩት አሃዞች የመላው ካፒታሊስት መደብ የሆነውን « ማንኛውንም የመዝገብ አያያዝ » ጠንካራ ገጽታ ያቀርባሉ ፤ የካፒታሊስቶችንም ብቻ አይደለም ፥ ምክንያቱም ባንኮች ለጊዜውም ቢሆን ማናቸውንም የግ ብር ገንዘብ — የትንንሽ ነጋዴዎችን ፤ የቢሮ ጸሐፊዎችን እና የጥቃቅን የሠራተኛውን መደብ የላይኛው ክፍል — ይሠበስባሉ ። « የምርት መገልገያ ሥርጭት» ከመደበ ኛው አንጻር በፈረንሣይ ከሶስት እስከ ስድስት እና ከጀ ርመን ከስድስት እስከ ስምንት ከሚደርሱ ባንኮች ውስጥ ወጥቶ በማደግ ብዙ ቢሊዮኖችን ነው የሚቆጣጠረው ። በይዘቱ ግን የምርት መገልገያዎች ሥርጭት ምንም ቢሆን «የጋራ ፤ » ሊሆን አይችልም ፤ የግል እንጂ ፤ ማለትም የትልቅ ወረት ፍላጐትን ቅርጽ ይይዛል ፤ እና በቅድሚያ የሕዝቡ ሠሪ ክፍል በችግር በሚኖርበት በኢንዱስትሪ ውስጥ « ከባድ ኢንዱስትሪዎች » በሌሎች ቅርንጫፍ ኢንዱስትሪዎች መግጠኛ ሲያስከፍሉ ለጠቅላላው የእ ርሻ ዕድገት ተስፋ በማጣት በኢንዱስትሪ ዕድገት ወደ ኋላ በሚቀርበት ሁኔታዎች ውስጥ የሚሠራውን ግዙፍ ሞኖፖሊ ወረት ቅርጽ ይይዛል ።

የካፒታሊስቱን ምጣኔ-ሀብት ሕብረተሰብአዊ በግ ድረት ጉዳይ ፤ የቁጠባ ባንኮችና የፖስታ ቤቶች ከባን ኮች ጋር ውድድር በመጀመር ላይ ናቸው ። የበለጠ «ግፅ ከላዊ ቢስ » ናቸው ፤ ማለትም በሥውር የሚገለገሉበት

ሥልጣን ፤ ቁጥራቸው በርከት ወዳለ ቀበሌዎች ፤ ወደ ጠረፍ ፤ ወደ የሕዝቡ ሠፊ ክፍሎች ፤ ተስፋፍቷል ። በባንኮችና በቁጠባ ባንኮች ውስጥ ስላለው የተጠራቀመ ተመዛዛኝ ዕድገት አንድ የአሜሪካ ኮሚሽን የሰበሰበው ሠንጠረዥ እነሆ[30] ።

የተጠራቀሙት /በቢልዮን ማርክ/

| | እንግሊዝ | | ፈረንሣይ | | ጀርመን | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | ባንኮች | የቁጠባ ባንኮች | ባንኮች | የቁጠባ ባንኮች | ባንኮች | የወለድ ኅብረተሰቦች | የቁጠባ ባንኮች |
| 1880 | 8.4 | 1.6 | ? | 0.9 | 0.5 | 0.4 | 2.6 |
| 1888 | 12.4 | 2.0 | 1.5 | 2.1 | 1.1 | 0.4 | 4.5 |
| 1908 | 23.2 | 4.2 | 3.7 | 4.2 | 7.1 | 2.2 | 13.9 |

በተጠራቀመው ላይ የ4ና የ4 1/2 እጅ በመቶ ሂሣብ ወለድ ስለሚከፍሉ ለወረታቸው « ትርፍ የሚያስገኙ » የሥራ መስኮችን መፈለግ አለባቸው ፤ በማስከፈያ ሠነዶች (ቢልስ) ፤ በመያዥያዎች (ሞርትጌጅስ)፤ ወዘተ . . . ማገልገል አለባቸው ። በባንኮችና በቁጠባ ባንኮች መካከል ያሉት መለያ መሥመሮች« የበለጠ እየጠፉ ይሄዳሉ» የቦሽምና የኤርፈርት የንግድ ምክር ቤቶች ለምሣሌ ፤ የቁጠባ ባንኮች እንደ ወለድ ክፍያን መቀነስ በመሣሠሉ « የባንክ ሥራ ንግድ » ላይ ከመሠማራት « እንዲከላከሉ» የፖስታ ቤት « የባንክ ሥራ » አገልግሎት ወሰን እንዲኖረው ይጠይቃሉ[31] ። የንግድ ሥራ ማህበሮች መንግሥታዊ ሞኖፖሊ ከማይጠረጠርበት ምሥጢራዊ ቦታ ይሰርቁናል ብለው የሚፈሩ ይመስላሉ ። ይሁን እንጂ ይህ ፍራቻ በአንድ ቢሮ የሚሠሩ በሁለት የቅርንጫፍ መስሪያ ቤት ማኔጆሮች ፤ መካከል ያለን ፉክክር መግለጫ ከመሆን

እንደማያልፍ የታወቀ ነው ። ምክንያቱም በአንድ ወገን ፤ ለቁጠባ ባንኮች በአደራነት የተሠጡት ቢሊዮኖች በነ ዚሁ የባንክ ካፒታል ማኅበሮች በራሣቸው ቁጥጥር ሥር ሲሆኑ በሌላ በኩል ደግሞ በካፒታሊስት ሕብረተሰብ ውስጥ ያለ መንግሥታዊ ሞኖፖሊ በአንድ ወይንም በሌ ላኛው ኢንዱስትሪ ውስጥ የሚገኙ በመክሰር ላይ ያሉ ሚሊየነሮች ገቢ እንዲያድግና መተማመኛ እንዲኖረው ማድረጊያ መሣሪያ ነው ።

የነጻ ውድድር የበላይ ከነበረበት የቀድሞው ካፒ ታሊዝም ፤ ሞኖፖሊ ወደ ነገሠበት ወደ አዲሱ ካፒታሊ ዝም የሚደረገው ለውጥ ፤ ሌላው ቢቀር በእቃዎች ልው ውጥ ጠቃሚነት ማሽቆልቆል ይገለጣል ። የዳይ ባንክ መጽሔት ሲገልጽ ፤ «የዕቃ ልውውጥ እንደማይገሠሥ አማ ካይ አዙዋዋሪ መሆኑን ባንኮች እጅግ ብዙ አዲስ ገንዘብ ለደንበኞቻቸው መስጠት ከመቻላቸው በፊት የነበረውን አሠራር ቀድሞውኑ አቁሟል ። » ብሏል[32] ። «እያንዳንዱ ባንክ እቃ አለዋዋጭ ነው ። ባንኩ እያደገና የባንክ ሥራ ክምችት እየተሣካ በሄደ መጠን የዚህ ዘመናዊ የብልጠት አባባል እውነተኛነት እየጨመረ ይሄዳል[33]። » «ቀደም ብሎ በሰባዎቹ ውስጥ ያዳዲስ ዕቃዎች ልውውጥ በብዛት ይጐ ርፍ ነበር ። (የኩባንያዎች ተንኮል ፤ ወ.ዘ.ተ. በ1873 የዕቃዎ ችን ልውውጥ በመሠረትነት ማንኮታኮታቸው «ለመገንዘብ የሚያስቸግር » መሆኑን መጥቀስ) አስመልክቶ የነበረው ውዝግብ « ተጨባጭ ባልሆነ አኳኋን » « ጀርመንን ኢንዱስትሪያዊ ያደረገውን ዘመን በር ከፍቷል ፤ በአሁኑ ጊዜ ባንኮችና ኢንዱስትሪዎች ለብቻቸው ለማካሄድ መቻላቸውን ያረጋግጣል ። » ታላላቅ ባንኮች በእቃ ልውውጥ ላይ ያደረሱት ተጽዕኖ ሌላ ነገር ሣይሆን ሙሉ በሙሉ የተደራጀው የጀርመን ኢንዱስትሪያዊ መንግሥት

መግለጫ ነው ። ሥራቸውን እንዳዘሏቸው ከመቅጽበት የሚያከናውኑት ምጣኔ—ሀብታዊ ሕግጋት የሥራ መስክ ፤ በዚህ ዓይነት እንዲወሰን ከተደረገ እና የስራ መስኮች ፤ በባንኮች የንቃት አሠራር ደንብ ሲካሄዱ እድ ገታቸው ከፍተኛ መስፋፋት በማሳየቱ የጥቂት የበላይ መሪዎች ብሔራዊ የምጣኔ - ሀብት ሃላፊነት ያለመጠን ያድጋል ።» ብሎ ይጽፋል[34] የጀርመኑ ፕሮፌሰር ሹልዝ ጋቨርነትዝ ። የጀርመን ኢምፔሪያሊዝም እርቅ ፈላጊ ፤ በመላ ኢምፔሪያሊስት ሃገሮች በዚህ ሃሣብ ከፍተኛ ተሰ ሚነት ያለውና « ዝርዝሩን ነገር » ማለትም ባንኮች ለም ጣኔ-ሀብታዊ ኑሮ የሚከተሉት « የንቃት አሠራር ደንብ» « በደንብ የተደራጁ » እፍኝ ሙሉ ሞኖፖሊስቶች ሕዝ ቡን መግፈፋቸውን ማጠቃለሉን ፤ ለመቀባባትና ለመ ሸፈን ይሞክራል ። የአንድ ቡርዧ ፕሮፌሰር ተግባር ፤ የውስጥ አሰራሩን ገላልጠ ማቅረብ ወይንም መላ የባንክ ሞኖፖሊስቶችን ተንኮል ማጋለጥ ሣይሆን እነሱን ተቀባ ይነት ሊያገኙ በሚችሉበት አኳኋን ማቅረብ ነው ።

በተመሣሣይ መንገድ ፤ ሪየዘር ፥ እንዲያውም የበ ለጠ ስልጣን ያለው ኤኮኖሚስትና እሱ ራሱ የባንክ ሠራ ተኛ ፤ የማይታበሉ ሀቆችን ለመግለጽ ትርጉም ከማይሰጡ ሐረጎች ይጉዳኛል ፥ « . . . . . . የብሔራዊ ምጣኔ ሀብቱ አስፈላጊ ፍጹም ገጽታ የሆነው የእቃ ልውውጦች ጥንካሬ እየላላ መሄዱ በአጠቃላይና የውእደቱ ደህንነት በተለይ ትክክለኛው የመለኪያ ዘንጉ ሳይሆን ግን ደግሞ የምጣኔ - ሀብቱን ቅጽበታዊ እንቅስቃሴዎች አንድነት ስርአት ባለው መንገድ ይቆጣጠራል[35] ።»

በሌላ አባባል የቀድሞው ካፒታሊዝም የዕቃዎችን ልውውጥ ሥርዓት ባለው መንገድ በነጻ ውድድር ይቆጣጠር የነበረው ካፒታሊዝም ፤ እየሞተ ነው ።

ግልጽ የሆነአንድ ዓይነት የመሸጋገሪያ ባሕርያት ያሉት ፤ የነጻ ውድድርና የሞኖፖሊ ቅይጥ ፤ አዲስ ካፒታሊዝም በቦታው እየተተካ ነው ። በተፈጥሮ ጥያቄዎች ይነሳሉ ፤ በምን ዓይነት ነው ይህ አዲስ ካፒታሊዝም « የሚአድገው » ? የሚለውን ጥያቄ ግን የቡርዧ ምሁራን ለማንሳት ይፈራሉ ።

« ከሠላሣ አመታት በፊት ነጋዴዎች እርስ በርሳቸው በነጻ በመወዳደር ከጉልበት ሥራዎቻቸው ውጪ ከንግዳቸው ጋር የተያያዘውን ሥራ ዘጠኝ አሥረኛውን አከናውነዋል ። በአሁኑ ጊዜ የዚህ « የአእምሮ ሥራ » « ዘጠኝ አሥረኛው በተቀጣሪዎች ነው የሚከናወነው ። የባንክ ሥራ የዚህ አዝጋሚ ዕድገት (ኢቮሉሽን) ግምባር ቀደም ነው[36] ።» ይህ ሹልዝ ጋቨርኒትዝ የሰጠው የእምነት ቃል በድጋሚ ወደ ጥያቄው ይወስደናል ፤ ይህ አዲሱ ካፒታሊዝም በኢምፔሪያሊስት ደረጃው ያለ ካፒታሊዝም ወዴት ነው የሚያድገው ?

በመድለብ ሒደት ምክንያት የመላው ካፒታሊስት ምጣኔ-ሀብት የበላይ ሆነው ከቆዩት ጥቂት ባንኮች መካከል ወደ ሞኖፖሊስት ስምምነቶች ፤ ወደ የባንክ ትረስት የሚያመራ እያደገ የሚሄድ አዝማሚያ ይታያል ። በአሜሪካ ፤ ዘጠኝ ግን አይደሉም ፤ ነገር ግን ሁለት ትልልቅ ባንኮች ፤ የቢሊየነሮቹ የሮክፌለርና የሞርጋን ፤ የአሥራ አንድ ቢሊዮን[37] ማርክ ወረት ይቆጣጠራሉ ። በጀርመን ቀደም ብለን የጠቀስነው የሻፍሀውዝንቬር ባንክቬሬይን በዲስኮንቶ — ጌስልሻፍት መዋጥ የዕቃዎች ልውውጥ ክፍየዎች ልሣን የሆነው ፍራንክፈርተር ጋዜጣ በሚከተለው አኳኋን ተችቶበታል ።

« የባንኮች የመድለብ እንቅስቃሴ ፤ ብድሮችን ሊያስገኙ የሚችሉትን ተቋሞች አካባቢ እያጠበበ ፤ ብሉም ፤

የትልቅ ኢንዱስትሪን በትንሽ የባንክ ሥራ ቡድኖች ላይ ጥገኛመሆኑ እየጨመረ ነው ። በኢንዱስትሪና በገንዘባ ዊው ዓለም መካከል የጠበቀ ግንኙነት በመኖሩ ምክን ያት ፤ የባንክ ወረት የሚፈልጉትን የኢንዱስትሪያዊ ኩባ ንያዎች የእንቅስቃሴ ነጻነት ያወስነዋል ። በዚህ ምክንያት፤ ትልቅ ኢንዱስትሪ ፤ እያደገ የሚሄደውን የባንኮች ወደ ትረስትነት መለወጥ በተደበላለቀ ስሜት ይከታተለዋል። በርግጥም ውድድርን ለማፈን የሚያልሙ አንዳንድ ትል ልቅ የባንክ ሥራ ኮንሰርኖች በመካከላቸው የሚያደርጓ ቸውን የአንዳንድ ስምምነቶች መጀመር ደጋግመን ተመ ልክተናል ።[38] »

በባንክ ሥራ መስፋፋት ውስጥ ተደጋግሞ የሚነገ ረው የመጨረሻው ቃል ሞኖፖሊ ነው ።

በባንኮችና በኢንዱስትሪ መካከል ያለውን የቀረበ ግንኙነት አስመልክቶ ፤ በትክክልም በዚህ አካባቢ ነው የባንኮች አዲስ ሚና ምናልባት ጠለቅ ብሎ የሚሰማ ። አንድ ባንክ የአንድን ተቋም ሠነድ በሚቀንስበት ጊዜ፤ ተንቀሳቃሽ ሂሳብ ሲከፍትለት ፤ ወ.ዘ.ተ. እነዚህን ሥራዎች ለያይተን ሥናያቸው ፤ ጥገኛ አለመሆኑን በምንም ዓይ ነት አይቀንሱትም ፤ ባንኩም ጨዋ አቀባባይ ከመሆኑ ሌላ የሚጫወተው ሚና የለውም። ይሁንና የዚህ ዓይነት ሥራዎች ከተባዙና ቋሚ ልምድ ኮሆኑ ፤ ባንኩ እጅግ ከፍተኛ መጠን ያለው ካፒታል በእጆቹ ውስጥ « በሚያ ያስገባባት » ጊዜ ፤ ለአንድ ተቋም የሚያደርገው የተን ቀሳቃሽ ሒሳብ መንቀሣቀስ ባንኩ የተሟላና ሰፊ መረጃ ስለደንበኞቹ ምጣኔ-ሀብት አቋም እንዲያገኝ ለማድረግ በሚቻልባት ጊዜ የሚሆነውም ይኸው ነው ፤ ውጤቱ የኢንዱስትሪያዊው ካፒታሊስት በባንኩ ላይ የበለጠ ሙሉ በሙሉ ጥገኛ መሆን ነው ።

እግረ መንገዱንም በባንኮችና በኢንዱስትሪዎች የን ግድ ተቋሞች መካከል እንበል የግለሰብ አንድነት ይፈ ጠራል ፤ በመካከል የባንክ ዲሬክተሮችን ፤ በኢንዱስት ሪያዊና የንግድ ተቋሞች ሱፐር ቫይዘር ቦርድስ( የዳይሬ ክተሮች ፤ ቦርዶች) በመመደብ እና በተዘዋዋሪው የአን ደኛውን ከአንደኛው ጋር መዋሃድ ይፈጥራል ። የጀር መኑ ኢኮኖሚስት ፤ ጄይደልስ ፤ ስለ እንደዚህ አይነቱ የወ ረትና የተቋሞች ድልበት ሠፋ ያለ ዝርዝር ጥናት አጠና ቋል ። ከበርሊን ትልልቅ ባንኮች መካከል ስድስት በ344 የኢንዱስትሪ ኩባንየዎች ውስጥ በዳይሬክተሮቻቸው ተወ ክለው ነበር ። በቦርድ አባሎቻቸው ደግሞ በ407 ሌሎች ኩባንያዎች ውስጥ ሲወከሉ በጠቅላላው በ751 ኩባንያ ዎች ውስጥ ተወክለዋል ። ከነዚህ ኩባንያዎች ውስጥ 2 89ኙ ወደ ሁለት ወኪሎች በያንዳንዱ ሱፐርቫይ ዘር ቦርዶች ውስጥ ይኖራቸዋል ፣ ወይንም የሊቀመንበር ነቱን ቦታ ይይዛሉ ። እነዚህን ኢንዱስትሪያዊና የንግድ ኩባንያዎች በጣም በተለያዩ የኢንዱስትሪ ቅርንጫፎች ውስጥ እናገኛቸዋለን ፤ በመድን ፤ በመጓጓዣ ፤ በምግብ ቤቶች (ታላላቅ)፤በቲያትሮች ፣ በኪነ ጥበብ እንዱስትሪ ፤ ወዘተ... በሌላ በኩል ፤ በነዚህ ስድስት ባንኮች (በ1910 ዓ. ም.) ሱፐርቫይዘሪ ቦርዶች ላይ ከታላላቅ ኢንዱስትሪ ያሊስቶች ሃምሣ አንዱ ፤ የክሩፐና ፤ የኃያሉ « ሃፓግ » (ሀምበርግ አሜሪካ መርከቦች) ዳይሬክተሮችን ፤ ወዘተ ... ጨምሮ ነበረበት ። ከ1895 ዓ. ም. እስከ 1910 ዓ. ም. እነዚህ ስድስት ባንኮች ፤ እያንዳንዳቸው ፤ የብዙ መቶ ኢንዱስትሪያዊ ኩባንያዎችን አክሲዮንና የሰነድ ሽያጭ እትሞች ላይ ተካፋይ ሆነዋል ። (ቁጥሩ ከ281—419 የሚ ደርስ)[39] ።

በባንኮቹና በኢንዱስትሪ መካከል ያለው የግለሠብ መተሳሰር የሚደገፈው በአገዛዙና በራሳቸው መካ

ከል ባለው የግለሰብ መተሳሰር ነው ። «በሱፐር ቫይዘር ቦርዶች ያሉት ቦታዎች » ይላል ጂይድልስ ሲጽፍ፤ «የሚሰጡት ማዕረግ ላላቸው እንዲሁም ደግሞ ከባለሥል ጣኖች ጋር ወዳጅነትን ለማስገኘት ጥረት ለሚያደርጉ የቀድሞ ሠላማዊ ሠራተኞች ነው ።» « . . . አብዛኛ ውን ጊዜ ፥ በአንድ ትልቅ ባንክ ሱፐርቫይዘር ቦርድ ላይ አንድ የፓርላማ አባል ወይንም ደግሞ አንድ የበርሊን ከተማ አማካሪ ይገኝበታል ። »

የታላላቅ ካፒታሊስት ሞኖፖሊዎች መገንባት ፥ በዓለም « የተፈጥሮ » እና « ከተፈጥሮ በላይ » በሆኑ መንገዶች በሙሉ ኃይሉ ወደፊት ይጓዛል ። በዘመናዊው የካፒታሊስት ሕብረተሰብ ላይ በነገሱ ፥ በብዙ መቶዎች የገንዘባዊ ንጉሶች መካከል አንድ አደነት የሥራ ክፍፍል እንዲያድግ እየተደረገ ነው ።

አንዳንድ ትልልቅ ኢንዱስትሪያሊስቶች ከሚያደ ርጉት የሥራ መስክ ማስፋፋት ፥ የባንኮች ቦርዶች አባል መሆን ፤ ወዘተ . . . « የክፍላተ ሃገርን የባንክ ማኔጀሮች በተወሰኑ የኢንዱስትሪ አካባቢዎች ከመመደብ ጋር አብሮ በአንድነት ፥ በትልልቆቹ ባንኮች ዲሬክተሮች መካከል የሙያ ክፍፍል እድገትም አለ ። በአጠቃላይ አነጋገር ፥ ይህ የሙያ ክፍፍል ሊታሰብ የሚችለው ፥ የባንክ ሥራ በከፍተኛ ደረጃ ሲካሄድና በተለይም ከኢንዱስትሪ ጋር የሥራ ግንኙነት ሲኖረው ነው ። የሥራ ክፍፍሉም በሁ ለት መሥመር ይጓዛል ፥ በአንድ ወገን ፥ ከኢንዱስትሪ ጋር የሚያደርጉት ግንኙነት በጠቅላላ ፥ አንድ የሥራ ክፍል በአንድ ዳይሬክተር ኃላፊነት ሥር ይተዋል ፥ በሌላ በኩል እያንዳንዱ ዳይሬክተር ፥ ተመሣሣይ ፍላጐት ያላቸውን ፥ ወይንም በአንድ ኢንዱስትሪ ቅርንጫፍ ውስጥ

ያሉ የተቋም ቡድኖች ፣ ወይንም በርካታ የተለያዩ ተቋ ሞችን የመቆጣጠሩን ተግባር ይወስዳል ። » (ካፒታሊ ዝም ፣ እያንዳንዱ ተቋሞች የተደራጀ ቁጥጥር የሚያገኙ በት ደረጃ ላይ ደርሷል ።) . . . . « አንዱ በጀርመን ኢንዱስትሪ ፣ አንዳንድ ጊዜም በምዕራብ ጀርመን ኢን ዱስትሪ ሙያ ብቻ ይሠለጥናል » (የምዕራቡ በጣም በኢንዱስትሪ የበለጸገ የጀርመን ክፍል ነው) ሌሎቹ ከውጪ መንግሥታትና ኢንዱስትሪ ጋር ባለው የግንኙ ነቶች ሙያ ፣ በኢንዱስትሪያሊስቶችና በሌሎች አቋም ላይ መረጃን በመሰብሰብ በሽቀጦች ልውውጥ ጥያቄዎች፤ ወዘተ ላይ ይሠለጥናሉ ። በተጨማሪም ፣ እያንዳንዱ የባንክ ዳይሬክተር ፣ ብዙ ጊዜ የተለየ አካባቢ ወይንም የተለየ የኢንዱስትሪ ቅርንጫፍ ይሠጠዋል ፣ አንዱ በይ በልጥ በኤሌክትሪክ ኩባንያዎች ፣ ሱፐርቫይዘሪ ቦርዶች ላይ እንዲሠራ ይደረጋል ፣ ሌላው በኬሚካል ፣ በቢራ መጥ መቂያ ወይንም በስኳር ድንች ፣ ሶስተኛው ፣ በጥቂት የተ ለያዩ የኢንዱስትሪ ተቋሞች ፣ ነገር ግን በመድን ኩባን ያዎች ሱፐር ቫይዘር ቦርዶች ላይ አብሮ እንዲሠራ ይደ ረጋል ። . . . . ባጭሩ ፣ የትልልቅ ባንኮች ሥራዎች በስፋትና በዓይነት ማደግ ከሥራ ክፍፍል ማደግ ጋር ተያይዞ የመጣ መሆኑ አያጠራጥርም ፤ ዓላማው (ውጤ ቱም) እንበል ፣ የባንክ ብቻ ከሆነ ሥራ በማላቀቅና እን ሱን ፣ በጠቅላላ የኢንዱስትሪ ችግሮችና በእያንዳንዱ ቅርንጫፍ ኢንዱስትሪ የተለዩ ችግሮች ላይ ጠበብት ፣ የተሻለ ግምት ያላቸው ለማድረግ ፣ ብሎም በየባንኩ የኢ ንዱስትሪ የተጽዕኖ አካባቢ በበለጠ እንዲሠሩ ለማስቻልም ሆነ በዳይሬክተሮቻቸው መካከል ያለውን የሥራ ክፍ ፍል ማስረግን ያስከትላል ። ይህ ሥርዓት ፣ ለሱፐርቫይ ዘሪ ቦርዶቻቸው እንደ ኢንዱስትሪያሊስቶች ፣ የቀድሞ

ባለሥልጣኖች ፣ በተለይም ቀድሞ በምድር ባቡር ወይ ንም በማዕድን ፤ ወዘተ አገልግሎት ይሠጡ የነበሩ ፣ የኢን ዱስትሪ ጉዳይ ጠበብትን ለመምረጥ ፣ ባንኮች በሚያደር ጉት ጥረት ይታገዛል ወ.ዘ.ተ. ወ.ዘ.ተ. »[40]

ጥቂት ይለየይ እንጂ በፈረንሣይ የባንክ ሥራም ተመ ሣሣይ ስርአት እናገኛለን ። ለምሣሌ ከሶስቱ የፈረንሣይ ታላላቅ ባንኮች አንዱ ፣ ክሬዲትሊዮኒ ፣ በቋሚነት ከሃ ምሣ በላይ መሐንዲሶች ፣ እስታቲሺያኖች ፣ ኤኮኖሚስ ቶች ፣ ጠበቆች ፣ ወዘተ . . . የቀጠረ ፣ አንድ የፊ ናንስ ምርምር አገልግሎት (ሰርቪስዲዝ ኤቱድ ፊናንሲየር) አደራጅቷል ። ይህ በዓመት ከስድስት እስከ ሰባት መቶ ሺህ ፍራንክ ወጪ ያስወጣል ። አገልግሎቱ በስምንት የቅርንጫፍ መሥሪያ ቤቶች ይከፈላል ፣ አንዱ የኢንዱ ስትሪ ተቋሞችን የሚመለከት መረጃ የመሰብሰብ ሙያ ያለው ፣ ሌላው ጠቅላላ ስታቲስቲክስ ያጠናል ፣ ሶስተ ኛው ስለ ምድር ባቡርና የእንፋሎት መርከብ ኩባንያ ዎች ፣ አራተኛው መተማመኛዎችን ፣ አምስተኛ ፊናንሲ ያዊ ዘገባዎችን ወዘተ . . . . . ያጠናሉ[41] ።

ውጤቱም ፣ በአንድ በኩል ፣ ከቅስከ እያደገ የሚ ሄድ ውህደት ፣ ወይንም ኢን. አይ. ቡካሪን በትክክል እንዳለው፣ የኢንዱስትሪና የባንክ ወረት መጣመር፣ እና በሌላ በኩል ፤ የባንኮች በርግጥ « አለም አቀፋዊ ጠባይ « ያላቸው ድርጅቶች ሆኖ ማደግ ናቸው ። በዚህ ጥያቄ ላይ ፣ ነገሩን በሚገባ ያጠናውን ፣ የጃይድልስን አባባሎች መጥቀስ አስፈላጊ ይመስለኛል ።

« የኢንዱስትሪ ዝምድናዎችን አጠቃላይ ምርመራ ማድረግ ፣ የኢንዱስትሪን ወክለው የሚሠሩትን ፊናንሣ ያዊ ተቋሞች ዓለም አቀፋዊ ጠባይ ግልጽ ያደርጋል ። እንደ ሌሎች ባንኮች ሳይሆን ፣ አንዳንድ ጊዜ በሥነ

ጽሑፍ ውስጥ ከተገለጠው ፣ ማለትም ባንኮች ውድ ቀት እንዳይመጣባቸው በአንድ የንግድ ሥራ ወይንም በአንድ የኢንዱስትሪ ቅርንጫፍ ሥራ መሠልጠን አለባቸው ከሚለው በተቃራኒ ፣ ትልልቅ ባንኮች ከኢ ንዱስትሪያዊ ተቋሞች ጋር ያሏቸውን ግንኙነቶች ፣ አካባቢና የኢንዱስትሪ ቅርንጫፍን በሚመለከት ፣ በተቻለ መጠን የተለዋወጡ እንዲሆኑ ይጥራሉ ፣ እና ፣ በእያንዳንዱ ተቋሞች የመስፋፋት ታሪክ ምክንያት ሊደ ርስ የሚችለውን በአካባቢዎችና በኢንዱስትሪ ቅርንጫ ፎች መካከል የወረት ሥርጭትን አለመሥተካከል ለማስ ወገድ ይጥራሉ ። » « አንዱ አዝማሚያ ፣ ከኢንዱስትሪ ጋር ያሏቸውን ግንኙነቶች አጠቃላይ ማድረግ ነው ፣ ሌላው አዝማሚየ ግንኙነቶችን ዘላቂና የጠበቁ ማድረግ ነው ። በስድስቱ ትልልቅ ባንኮች እነዚህ ሁለት አዝማ ሚያዎች ሙሉ በሙሉም ባይሆን ፣ በእኩል ደረጃና ከፍ ተኛ ግምት ሊሰጠው በሚችል አኳኋን ተፈጽመዋል ። »

የኢንዱስትሪና የንግድ አካባቢዎች ፣ ደጋግመው በባንኮች « ሽብር » ላይ ተቃውሞ አሰምተዋል ። ከሚቀ ጥለው ምሳሌ ለማየት እንደሚቻለው ፣ የዚህ ዓይነቶቹ «ተቃውሞዎች ፣ » ለትልልቅ ባንኮች « እዝ » መድረ ሳቸው እያስ፤ ንቅም ። በኅዳር 19 ቀን 1901 ዓ. ም. በር ሊን ዲ በመባል የሚታወቀው ከትልልቅ ባንኮች አንዱ (የአራቱ በጣም ትልልቅ ባንኮች ስሞች በዲ ይጀምራሉ) ለጀርመን ማዕከላዊ የሲሚንቶ ሲንዲኬት (ጀርመን ሴን ትራል ሲመንት ሲንዲኬት) የዳይሬክተሮች ቦርድ ፣ በሚ ከተለው አባባል ይጽፋል ፣ « በአንድ የ18ኛው በሆን ጋዜጣ ምሳሌ ካሳተማችሁት ማስታወሻ ማወቅ እንደቻልነው ፣ ሲንዲኬታችሁ የሚቀጥለው ፣ በዚህ ወር በ30ኛው ዕለት የሚደረገው ጠቅላላ ስብሰባ በሥራችሁ ውስጥ ለውጦችን

ሊያመጡ በሚችሉ ፣ በኛ በኩል ተቀባይነት በማይኖራቸው እርምጃዎች ላይ አቋም ይወስድ ይሆናል ። በነዚህ ምክንያቶች ፣ ከዚህ በኋላ ከአሁን በፊት ተፈቅዶላችሁ የነበረውን ብድር ለመመለስ ለመገደዳችን የጠለቀ ሀዘን ይሰማናል ። . . . ይሁንና ፣ የተባለው የሚቀጥለው ጠቅላላ ስብሰባ ለኛ በማይስማሙ እርምጃዎች ላይ አቋም የማይወሰድ ከሆነና በዚህ ጉዳይ ላይ ለወደፊቱ ተስማሚ መተማመኛ የምናገኝ ከሆነ ፣ ከናንተ ጋር ፣ አዲስ የሚሰጥ ብድርን በሚመለከት ድርድር ለመክፈት ዝግጁ ነን ።[42]»

እንደ እውነቱ ከሆነ ይህ ፣ በትልቅ ካፒታል ስለመጨቆኑ አንድ ትንሽ ካፒታል የቀረበው ያረጀ ተቃውሞ ነው ፤ ነገር ግን እዚህ ላይ መላው ሲንዲኬት ነው « በትንሽ » ካፒታል ደረጃ የተመደበው ። ቦትንሽና በትልቅ ወረት መካከል ይደረግ የነበረው የቀድሞው ትግል ፣ በአደገ መጠን በሌላው ከፍተኛ የዕድገት ደረጃ መካሔድ እየጀመረ ነው ። የትልላቅ ባንክ ተቋሞች በቢሊዮን የሚገመቱ የሚወጡት ፣ ከቀድሞዎቹ ሊወዳደሩ በማይችሉ ምንጮችና መሣሪያዎች የቴክኒክ መስፋፋትን ሊያፋጥኑ መቻላቸው ያለምክንያት አይደለም። ባንኮች ለምሣሌ፤ ልዩ የቴክኒክ ምርምር ሕብረተሰቦችን ያቋቁማሉ፣እና በርግጥም ፣ « ወዳጅ የሆኑ » የኢንዱስትሪ ተቋሞች ብቻ ናቸው በውጤቱ ሊገለገሉ የሚችሉ ። የኤሌክትሪክ ባቡር የምርምር ማኅበር ፣ የሣይንሣዊና ቴክኒካዊ ምርምር ማዕከላዊ ቢሮ ፣ ወዘተ . . . ከዚህ ክፍል ይመደባሉ ።

የትልልቅ ባንኮች ዲሬክተሮች ራሳቸው ፣ አዳዲስ ብሔራዊ የምጣኔ ሀብት ሁኔታዎች እየተፈጠሩ መሆናቸውን ማየት አይሳናቸውም ፣ ነገር ግን በነዚህ ክስተቶች ፊት ምንም ኃይል የላቸውም ።

« ማንም ፣ ከጥቂት አመታት ወዲህ » ይላል ጅይ ድልስ ሲጽፍ « የሐላፊነት ወንበሮች (ሥልጣን) ና በት ልቅ ባንኮች ሱፐርቫይዘሪ ቦርዶች የተደረጉትን ለውጦች ሲከታተል የቆየ ፣ ሥልጣን ቀስ በቀስ ፣ በጠቅላላ የኢን ዱስትሪ መስፋፋት ፣ ትልልቅ ባንኮች ጣልቃ መግባታ ቸው አስፈላጊና ጠቃሚም ነው ብለው ወደሚገምቱ ሰዎች ፣ እየተላለፈ መሆኑን ፣ ማስታወስ አይሣነውም ። በነዚህ በአዲሶቹ ሰዎችና በቀድሞ የባንክ ዳይሬክተሮች መካከል ፣ በዚህ ጉዳይ ላይ፣የንግድና የግል አለ መግባባቶች በተደጋጋሚ እያደጉ ናቸው ። የጸቡ መነሾ ፣ ባንኮች የብ ድር ድርጅቶች እንደመሆናቸው ፣ በኢንዱስትሪ ጣልቃ በመግባታቸው መከራ ያጋጥማቸው አያጋጥማቸው ብድር በመስጠት እንደ አቀባባይ ከሚጫወቱት ሚና ጋር ምንም አይነት ግንኙነት በሌለው የሥራ መስክ የተፈተኑ መርሐ ግብሮችንና የተረጋገጠ ትርፍን አሳልፈው ይሰጡ ወይ አይሰጡ እና የትኛው ነው ባንኮችን ከመቸውም የበለጠ ወደ ዓይን ያጡ የንግድ ውጣ ውረዶች መስክ የሚመ ራቸው ? የሚለው ነው ። ይህ የቀድሞዎቹ የባንክ ዳይሬ ክተሮች ሃሣብ ሲሆን ፣ አብዛኛዎቹ ወጣት ሰዎች ደግሞ ፣ ከትልቅ ዘመናዊ ኢንዱስትሪ ጋር አብሮ ፣ ለትልልቅ ባን ኮችና ለኢንዱስትሪያዊ የባንክ ሥራ መነሻ የሆነው ነገር አስፈላጊ የሆነውን ያህል ፣ በኢንዱስትሪ ጣልቃ ገብነት አስፈላጊ መሆኑን ይገምታሉ ። ሁለቱ ፓርቲዎች በአ ንድ ነጥብ ላይ ብቻ ይስማማሉ ፣ እነሱም ጠንካራ መርሃ ግብሮች ወይም በትልልቆቹ ባንኮች አዲስ ከንዋኔዎች ተጨባጭ ዓላማ አለመኖር ናቸው [43] ።

የቀድሞው ካፒታሊዝም ቀን አልፎበታል ። አዲስ ካፒታሊዝም ወደ አንድ ነገር መሸጋገሪያን ይወክላል ። ሞኖፖሊን ከነጻ ውድድር « ለማስታረቅ » « የማይነቃ ነቁ መርሐ ግብሮችንና ጠንካራ ዓላማን » መሻት በርግጥ

ተስፋ ቢስ ነው ። ተግባራዊ ሰዎች የሚያደርጉትን አምኖ መቀበል ፥ ለተደራጀ ካፒታሊዝም ፥ በእርቅ ፈላጊዎቹ ሹልዝ ጋቨርኒትዝ ፥ ሊየፍማንና ተመሳሳይ « ንድፈ ሐሣባውያን » ከሚዘመረው ይራ የወጣ ምሥጋና ፥ የተለየ ቦታ አለው ።

የትልልቅ ባንኮች « አዳዲስ ተግባራት » በመጨረሻ የተመሠረቱት በትክክል ምን ጊዜ ነበረ ? ለዚህ ጠቃሚ ጥያቄ ፥ ጄይደልስ ፥ ከሞላ ጐደል ትክክለኛ የሆነ መልስ ይሰጠናል ።

« በባንኮችና በኢንዱስትሪያዊ ተቋሞች መካከል ያሉት ዝምድናዎች ፥ ከአዲሱ ይዞታቸው ፥ ቅርጻቸውና ፥ ብልቶቻቸው ማለትም ፥ ማዕከላዊና ማዕከላዊ ባልሆነ መንገድ የተደራጁት ትልልቅ ባንኮች ፥ ጋር ፥ ከዘጠናዎቹ በፊት ይህንን ያህልም የምጣኔ ሀብት ክስተት ጠባይ አልታየባቸውም ፤ በአንድ አይነት አመለካከት ፥ በርግጥም ፥ ይህ የመጀመሪያ ዕለት ወደ 1897 ሊሸጋሸግ ይችል ይሆናል ፥ ይህም ጠቃሚ « ውህደቶች » የተፈጸሙበትና ለመጀመሪያ ጊዜ ፥ ለባንኮች ኢንዱስትሪያዊ ፖሊሲ ለመስማማት ፥ አዲሱ ዓይነት ኢማዕከላዊ ድርጅት ሥራ ላይ የዋለበት ጊዜ ነው ። ይህን የመጀመሪያ ነጥብ ፥ እንዲያውም ምናልባት ከዚህ ወደ ቀረበ ዕለት ማምጣት ይቻል ይሆናል ። ምክንያቱም ፥ የባንክ ሥራንና የኢንዱስትሪን የመድለብ ሒደት በጣም ያፋጠነውና ያጧጧፈው ፥ የጠናከረው ፥ ለመጀመሪያ ጊዜ ከኢንዱስትሪ ጋር ያለውን ግንኙነት ፥ ወደ ትልልቅ ባንኮች ትክክለኛ ሞኖፖሊ የቀየረውና ይህንንም ግንኙነት የቀረበና በይበልጥ እንዲሠራ ያደረገው ፥ የ1900 ቀውስ ስለነበረ ነው ።[44]»

ስለዚህ ፥ ሃያኛው ምዕተ ዓመት ፥ ከቀድሞው ካፒታሊዝም ወደ አዲሱ ፥ ከጠቅላላ የወረት ገዥነት ወደ ግንዘባዊ ወረት ገዥነት ሽግግር የተደረገበት ወቅት ነው ።

# ምዕራፍ ፡ 3

## ገንዘባዊ ወረትና ገንዘባዊ ሥልጣን(የጥቂት ሞኖፖሊስቶች ሥልጣን መያዝ)

«እየተጠናከረ የሚያድገው በኢንዱስትሪ ውስጥ ያለው ወረት መጠን» ይላል ሂልፈርዲንግ ሲጽፍ «የሚገለገሉበት ኢንዱስትሪያሊስቶች ንብረት መሆኑን ያቆማል ። ኢንዱስትሪያሊስቶቹ የወረታቸውን ጥቅም የሚያገኙት ፣ ከነርሱ ጋር ባላቸው ግንኙነት በሚወክሏቸው በባንኮች አለዋዋጭነት (አዘዋዋሪነት) ነው ። በሌላ በኩል ፣ ባንኩ ፣ እያደገ የሚሄደውን የገንዘቡን አክሲዮን በኢንዱስትሪ ውስጥ ሥራ ላይ ለማዋል ይገደዳል ። ስለዚህ ፣ ባንከኛው፣ በማያቋርጥ መጠን ወደ ኢንዱስትሪያዊ ካፒታሊስትነት እየተለወጠ ይሄዳል ። ይህን የባንክ ወረት ማለትም በገንዘብ መልክ ያለ ወረት ፣ ወደ ኢንዱስትሪያዊ ወረትነት በትክክል የተለወጠ ወረት ፣ የገንዘብ ወረት ብዬ እጠራዋለሁ ።» «የገንዘብ ወረት ማለት በባንኮች ቁጥጥር ሥር ያለውና ኢንዱስትሪያሊስቶች የሚገለገሉበት ወረት ነው ።»

ይህ ትንታኔ ፣ በጣም[45] ጠቃሚ ስለሆነ ሀቅ ምንም ስለማያወሳ የተሟላ አይደለም ። ይኸውም ፣ የምርትና የወረት መድለብ በከፍተኛ ደረጃ አድጎ ወደ ሞኖፖሊ እንደሚያመራና እያመራም መሆኑን አለመጥቀሱ ነው ። ይሁን እንጂ ፣ በጠቅላላው በመጽሐፍ ውስጥ በተለይም ይህ ትንታኔ ከተወሰደበት ምዕራፍ ቀደም ብለው ባሉት ሁለት ምዕራፎች ውስጥ ሂልፈርዲንግ ፣ ካፒታሊስት ሞናፖሊዎች የተጫወቱትን ሚና አበክሮ ይጠቅሳል ። የም

ርት መድለብ ፣ ከዚህም የሚመጡት ሞኖፖሊዎች ፣ የባ ንኮች ከኢንዱስትሪ ጋር መዋሀድ ወይንም መጣመር ፣ እንደዚህ ነው የገንዘብ ወረት አመጣጥ ታሪክና የቃሉ ይዘት ፣ ከእንግዲህ ወዲያ ፣ በሸቀጥ ምርትና በግል ባለን ብረትነት አጠቃላይ ሁናቴ ውስጥ ፣ የኮፒታሊስት ሞና ፖሊዎች « የሥራ እንቅስቃሴዎች » የገንዘባዊ ሥልጣን ተፅዕኖ መሆኑ እንደማይቀር እንዴት እንደሆነ ማብራ ራት አለብን ። እንደ ሪየዘር ፣ ሹልዝ ጋቨርኒትዝ ፣ ሊየፋ ማንና የመሳሰሉት የጀርመንና የጀርመን ቡርዧ ምሁራን ወኪሎች ብቻ አይደሉም ፤ የሁሉም የኢምፔሪያሊዝምና የገንዘባዊ ወረት ይቅርታ ጠያቂዎች መሆናቸው መታወስ አለበት ። የገንዘባዊ ሥልጣን አመሠራረትን « ሜካኒ ክስ ፣ ዘዴው ፣ » «ተንኰል በሆነና ባልሆነ » የሚያገኘውን የዓመት ገቢ መጠን ከፓርላሜንቶች ጋር ያለውን ግንኙ ነቶች ወዘተ ፣ ይፋ በማውጣት ፈንታ ያጨልሙዋቸዋል እና ያድበሰብሱታል ። እነዚህን « የጦፉ ጥያቄዎች » ግርማ ባላቸውና ግልጽ ባልሆኑ ሐረጎች በመጠቀም የባንክ ዳይሬክተሮችን « የኃላፊነት ስሜት » በመማጸን ፣ የፕሩ ሲያን ባለሥልጣኖች « የሥራ ስሜት » በማድነቅ ፣ ሞና ፖሊዎችን ለመቆጣጠርና « ለመደንገግ » የሚረዱ ትን ፣ ፍጹም አስቂኝ የሆኑትን የፓርላማ ህጎች ጥቃ ቅን ሀተታዎች ኮስተር ብሎ በማጤን ፣ በንድፈ ሐሣቦች ጋጋታ በመጫወት ፣ ለምሣሌ ቀጥሎ እንደ ቀረበው የፕሮፌሰር ሊየፍማን « ሣይንሣዊ » አቀ ራረብ ያለውን « የንግድ ሥራ ፣ ዓላማው ዕቃዎችን መሰ ብሰብ ፣ ማከማቸትና ለተጠቃሚዎች ማቅረብ የሆነ አንድ የሥራ ዘርፍ ነው[46] ፣» (ሥርዝ የፕሮፌሰሩ) የመሳሰሉትን ዓይነት ትንታኔ በማቅረብ ፤ ወዘተ .... ይሸፉዋቸዋል ። ከዚህ መረዳት የሚቻለው ፤ የንግድ ሥራ በጥንት ጥን

ታዊ የጋርዮሽ ሰው ጊዜ (ስለልውውጥ ምንም የማያቅ) የነ በረ በሶሽያሊዝምም ውስጥ ሊኖር የሚችል ነው እንደማ ለት መሆኑን ነው ።

ይሁንና ፣ የገንዘባዊ ሥልጣንና ጭካኔአማውን ሕግ አስመልክቶ ያሉት ግዙፋን ሐቆች ደምቀው ፣ ገጠው የሚታዩ በመሆናቸው ፣ በሁሉም የካፒታሊስት ሀገሮች በአሜሪካ ፣ በፈረንሣይና በጀርመን ፣ ከቡርዧ አመለካ ከት አንጻር የቀረበ ፣ ነገር ግን ስለገንዘባዊ ሥልጣን በመ ጠኑም ቢሆን እውነተኛ ገጽታና ሂስ — የንዑስ ከበርቴም ቢሆን ፣ የሚሰጥ ሠፊ ሥነ ጽሑፍ ቀርቧል ።

ከዚህ በፊትባጭሩ ከላይ የተጠቀሰው « የአያያዝ ሥርዓት » ከፍተኛ ግምት የሚሰጠው ነው ። የጀርመኑ ኤኮኖሚስት ፣ ሄይማን ፣ ምናልባትም ይህንን ነገር ይፋ ለማ ውጣት የመጀመሪያው ሰው የሆነው ፣ ጽንሰ ሐሣቡን እን ዲህ ሲል ይገልጸዋል ፣ «የኮንሰርኑ የበላይ ኃላፊ ዋናውን ኩባንያ ይቆጣጠራል »

በተራ አባባል « እናት ኩባንያውን » ፤ « ዋናው ኩባንያ በቅርንጫፍ ኩባንያዎች ላይ ይነግሳል » « (በልጅ ኩባንያዎች ላይ») «እነዚህ በበኩላቸው የቅርንጫፍ ቅርን ጫፍ የሆኑትን ይቆጣጠራሉ» «የልጅ ልጆቹን ማለት ነው» ወዘተ . . . «በዚህ መንገድ ፣ በአነስተኛ ወረት ፣ በጣም ሰፊ የማምረቻ አካባቢዎችን በቁጥጥር ሥር ለማ ድረግ ይቻላል ። በርግጥም ፣ አንድን ኩባንያ ለመቆጣ ጠር የወረቱ 50 በመቶ እጅ ሁልጊዜ ለመያዝ በቂ ከሆነ የኮንሰርኑ የበላይ ኃላፊ ፣ በሁለተኛው ቅርንጫፍ ያለውን ስምንት ሚሊዮን ለመቆጣጠር ፣ አንድ ሚሊዮን ብቻ

ይበቃዋል ። ከዚያም ይህ መቆላለፍ እየሰፋ ሲሔድ በአ ንድ ሚሊዮን ፤ አሥራ ስድስት ሚሊዮን ፣ ሠላሣ ሁለት ሚሊዮን፤ ወዘተ ለመቆጣጠር ይቻላል [47] ። »

እንደ እውነቱ ከሆነ ፣ ከልምድ እንደታየው የአንድን ኩባንያ አሠራር ለመምራት የኩባንያው 40 እጅ በመቶ የአ ክሲዮን ባለቤት መሆን ብቻ ይበቃል[48] ። ምክንያቱም የተ ወሰኑ ጥቂት በየቦታው የሚገኙ ባለአክሲዮኖች በጠቅ ላላ ስብሰባዎች ላይ ለመገኘት ፣ በተለምዶ ስለማይ ችሉ ፤ ወዘተ . . ነው ። የቡርዧ አወናባጆችና « ሶሺያል ዲሞክራቶች » እየተባሉ የሚጠሩት አድርባዮች ፣ ከሱ ተነስተው « የወረትን ዲሞክራሲያዊነት መሆን » የአነስተኛ ደረጃ ምርትን ጥቅምና ሚና ማጠናከር ፤ ወዘተ ፣ . . . እንዲደረጉላቸው የሚመኙበት የአ ክሲዮኖች ባለቤትነት ዲሞክራሳዊነት መደረግ ፣ የገን ዘባዊ ሥልጣንን ኃይል ከሚጨምሩት መንገዶች አንዱ ነው ። በነገራችን ላይ ፣ በጣም በሰለጠኑት ወይም ጥን ታዊና የበለጠ « ልምድ » ባላቸው የካፒታሊስት ሀገሮች ውስጥ አክሲዮኖች በአነስተኛ ክፍያ እንዲታደሉ ሕግ ይፈቅዳል ። በጀርመን ሀገር ፣ አክሲዮኖች ከአንድ ሺህ ማርክ ክፍያ በታች እንዳይታደሉ በህግ የተከለከለ በመ ሆኑ የጀርመን ገንዘባዊ ማሕበሮች የአንድ ፓውንድ (20 ማርክ በግምት 10 ሩብል) አክሲዮን ሊሰጥ የሚቻልበትን እንግሊዝን በቅናት ዓይን ይመለከታታል ። ከታላለቅ የጀ ርመን ኢንዱስትሪያሊስቶችና « የገንዘባዊ ንጉሶች » አንዱ ሲመንስ ፣ ሰኔ 7/1900 ዓ. ም. የአንድ ፓውንድ አክሲዮን የእንግሊዝ ኢምፔሪያሊዝም መሠረት መሆኑን ለፓርላማው ገልጧል[49]። ይህ ነጋዴ ፣ ከአንዳንድ የሩሲያ

ከማርሲዝም መሥራች ዘረቢስ ጸሐፊና ኢምፔሪያሊዝም የአንዳንድ ሀገሮች መጥፎ ልምድ ነው ከሚለው የተሻለ ስለኢምፔሪያሊዝም ጠለቅ ያለና የበለጠ « ማርክሳዊ » የሆነ እውቀት አለው ።

ይሁንና « የመያዣው ሥርአት» የሞኖፖሊስቶችን ኃይል በከፍተኛ ደረጃ ከማሳደጉም በላይ ፥ ሞኖፖሊስቶቹ ሕዝቡን ለማታለል ፥ በማናቸውም የተድበሰበሱና ርካሽ የማጭበርበሪያ ዘዴዎች እንዲጠቀሙ ያስችላቸዋል ። ምክንያቱም « የናት ኩባንያው » ዳይሬክተሮች « ለግል ገል ኩባንያው » ሕጋዊ ኃላፊዎች አይደሉም ፥ «ራሱን የቻለ» ነው ስለሚባልና በርሱም አማካይነት ማናቸውንም ነገር ሊያገኙ ስለሚችሉ ነው ። ከጀርመን ሪቪው ዳይባ ንክ ግንቦት 1914 የተገኘ ምሣሌ እነሆ ፤

« የካስል የስፕሪንግ የዐረብ ብረት ኩባንያ፥ ከጥቂት ዓመታት በፊት ፥ በጀርመን ከፍተኛ ትርፍ ከሚያስገኙት ኩባንያዎች አንዱ ነው እየተባለ ይገመት ነበር ። በመጥፎ አመራር ምክንያት ያገኘው የነበረው ትርፍ ከ15 እጅ በመቶ ወደ ምንም ወረደ ። እንደሚታየው ቦርዱ ባለአክሲዮኖችን ሳያማክር «ከግልገል ኩባንያዎች» ለአንደኛው ፥ ለስሙ የጥቂት መቶ ሺህ ባለካፒታል ለሆነው ፥ ሃስያ ሊሚትድ ለሚ ባለው ስድስት ሚሊዮን ማርክ አበድሯል ። « የእናት ኩባንያው » ወረት ሶስት እጅ የሚሆነውን ፥ ይህን ያህል ገንዘብ ለመሥጠት የተደረገው ስምምነት በመተማመኛው ሠነድ (ባላንስ ሺት) ላይ ፈጽም አልተጠቀሰም ነበር ። አለመጠቀሱ ለሁለት ዓመት ሙሉ ዝም ተብሎ ሊታለፍ መቻሉ ሕጋዊ ነበር ፥ ምክንያቱም የኩባንያውን ሕግ ያል ተላለፈ ስለነበር ። እንደ የበላይ ኃላፊነቱ ፥ ያልተስተካ ከለው ሠነድ ላይ የፈረመው የሱፐርቫይዘሮች ቦርድ ሊቀ

መንበር ፣ የካስል የንግድ ምክር ቤት ፕሬዚዳንት ነበረ ፣ አሁንም ነው ። ባለአክሲዮኖቹ ፣ ለሃስያ ሊሚትድ ስለ ተሠጠው ብድር ፣ ብዙ ጊዜ ቆይተው ፣ ሥህተት መሆኑ ከተረጋገጠና የስፐሪንግ ስቲል አክሲዮን መቶ በመቶ ከወደቀ በኋላ ፣ ምክንያቱና ጉዳዩን የሚያውቁትን አባ ሯቸው ስለነበር ነው ሊሠሙ የቻሉት ። (ስህተት የሚ ለውን ቃል ጸሐፊው በትምህርተ ጥቅስ ውስጥ ማስገባት ነበረበት )

ይህ ፣ ዓይነተኛ የማመዛዘኛ ሰነድ አሻጥር ፣ ውሁድ ድብል ኩባንያዎች ውስጥ የተለመደ ፣ ለምን የዳ ይሬክተሮቻቸው ቦርዶች ፣ ከግል ነጋዴዎች ይልቅ በአ ደገኛ የንግድ ሥራ ውስጥ ብዙም ሳይጨነቁ እንደሚዘ ልቁ ያስረዳል ። የዘመኑ የማመዛዘኛው ሰነዶች ማዘጋጃው ዘዴ ፣ ከማንኛውም ባለአክሲዮን ፣ የሚያጠራጥሩ አሠ ራሮችን ለመሠወር ከማስቻሉም በላይ ፣ በአሻጥሩ የተዘ ፈቁት ግለሰቦች ፣ በጊዜ አክሲዮናቸውን ሸጠው ሊደርስ ባቸው ከሚችለው መጥፎ ነገር ሊያመልጡ እንደሚችሉ ያደርጋል ። በሌላ በኩል ግን የግለሰብ ነጋዴዎች የሚ ሠሩት ሥራ ለሚያመጣው ጉዳት ኃላፊ የሚሆኑት እነ ሱው ናቸው ።

« የብዙ ውሁድ ድብል ኩባንያዎች ማመዛዘኛ ሰነዶች የሰነዱን ትክክለኛ ትርጉም የሚሠጠውን ከሥር ያለውን ጽሑፍ ለማግኘት ፣ ከላይ ያለውን ፣ የሚታየውን ጽሑፍ ማጥፋት የሚያስፈልጋቸውን የመካከለኛውን ዘመን የብራና ጽሑፎች ያስታውሱናል ። » ( ብራና ጽሑፎች ( Patumpsests ) መጀመሪያ ተጽፎባቸው የነበረው ነገር እንዲጠፉ ተደርጐ በጠፋው ላይ ሌላ የሚጻፍባቸው የብ ራና ሠነዶች ናቸው ) ።

«የማመዛዘኛ ሰነዶች ፣ ምሥጢራቸው እንዳይፈታ ግድረጊያው ቀላሉና ዘወትር የሚጠቀሙበት መንገድ ፣ አንድን ነጠላ ኩባንያ « ግልገል ኩባንያዎችን » በግዳጳም ከብዙ ቦታ መከፋፈል ወይም ቀድሞ የተቋቋሙትን መጠቅለል ነው ። ለብዙ ዓላማዎች — ህጋዊና ከሕግ ውጪ ለሆኑ የዚህ አሠራር ጥቅሞች ግልጽ ከመሆናቸው የተነሳ ፣ በሱ የማይጠቀም ከትልቅ ኩባንያዎች ውስጥ ማግኘት ያልተለመደ ነው[50] ።»

ይህን ሥርዓት በሰፊው ለሚገለገሉበት ትልልቅ ሞኖፖሊስት ኩባንያዎች እንደ ምሣሌ ዶራሲው የጠቀሰው ዝነኛው የጄኔራል ኤሌክትሪክ ኩባንያ ( እኛም በሌላ ጊዜ የምንጠቅሰው) ነው ። በ1912 ዓ. ም. ይህ ኩባንያ ፣ ከ175 እስከ 200 በሚደርሱ ሌሎች ኩባንያዎች ውስጥ አክሲዮን ነበረው ፣ በተጽዕኖው ሥርም አውሏቸው ስለነበረ በግምት 1.500,000,000 ማርክ የሚደርስ ጠቅላላ ወረት ይቆጣጠርነበር[51] ።

ከመቆጣጠሪያ ህጐች አንዳቸውም እንኳ የማመዛዘኛ ሠነዶችን ማሣተም ፣ የማመዛዘኛ ሰነዶችን በአንድ በተወሰነ መልክ ማዘጋጀት ፣ ሂሳቦችን በሕዝብ ኦዲት መደረግ ፤ ወዘተ ....፣ ጠንካራ ዓላማ ያላቸው ፕሮፌሰሮችና ባለሥልጣናት ማለትም ለካፒታሊዝም ጥብቅና በመቆምና እሱን በማወደስ በጠንካራ ዓላማ የተጠመቁት ለሕዝቡ የሚደረጉት ንግግሮች ፣ የሚጠቅሙ አይደሉም ። ምክንያቱም ፣ የግል ንብረት ቅዱስ ነው ፣ እናም ፣ ማንም አክሲዮኖችን ከመግዛት ፤ ከመሸጥ ፤ ከመለወጥ ወይም ለዕዳ ከማስያዝ ወዘተ አይከለክልምና ።

« የመያዣ ሥርዓት » በሩሲያ ባንኮች እንዴት እን ዳደገ ፣ ለአሥራ አምስት ዓመታት የሩሲያና የቻይና ባንክ ባለሥልጣን የነበረውና በግንቦት ወር 1914 ዓ. ም. ትክ ለኛ ርዕሱም ባይሆን ታላላቅ ባንኮችና የአለም ገበያ የሚል መጽሐፍ ያሳተመው ፣ ኢ. አግሐድ ከሠጠው አሐዝ መረ ዳት ይቻላል[52]። ደራሲው የሩሲያን ባንኮች በሁለት ዋና ዋና ክፍሎች ከፍሏቸዋል ። ሀ/ « በመያዣ ሥርዓት » ሥር ያሉ ባንኮችና ለ/ « ጥገኛ ያልሆኑ » ባንኮች ። ይሁን እንጂ « ጥገኛ አለመሆን የሚለው ቃል እንዲሁ በዘፈቀደ በ ውጪ ባንኮች ላይ » ጥገኛ አለመሆን ለማለት የተወሠደ ነው ። ደራሲው የመጀመሪያውን ክፍል መልሶ በሶስት ንዑስ ክፍሎች ከፍሎታል ። 1/ የጀርመን ይዞታዎች 2/ የእንግሊዝ ይዞታዎችና 3/ የፈረንሣይ ይዞታዎች ናቸው ።

ይህንንም ሲያደርግ የተጠቀሱት ሀገሮች ታላላቅ ባንከን ተፅዕኖና ይዞታዎች እያውጠነጠነ ነው ። ደራ ሲው የባንኮችን ወረት ለምርት አገልግሎት ሥራ ላይ በማዋልና (በኢንዱስትሪያዊና የንግድ ተቋሞች) እና ዋጋ በመለወጥ ትርፍ ለማግኘት ድብሎችን በመሸጥና «በመግዛት» ዓላማ ሥራ ላይ በሚውል ወረት(የሸቀጥ ልውውጥ ገንዘባዊ የንግድ ሥራ) በሚል ሁለት ቦታ ከፍ ሎታል ።ይህንንም ሲያደርግ በንዑስ ከበርቴ የጠጋኝ አመ ለካከቱ ፣ በካፒታሊዝም ውስጥ የመጀመሪያውን ዓይ ነት የወረት አወጣጥ ከሁለተኛው ሊገነጥልና ሁለተኛ ውን ፈጽሞ ለማጥፋት እንደሚቻል በመገመት ነው ። እሱ የሚያቀርባቸው አሐዞች እነሆ ።

# የባንክ ንብረቶች /አሴቶች/

## /ከጥቅምት—ኅዳር 1913 ዓ ም በቀረበው ዘገባ መሠረት /

## በሚሊዮን ሩብሎች

| የሩሲያ ባንክ ክፍሎች | ሥራ ላይ የዋለው ወረት | | |
|---|---|---|---|
| | ለምርት አገልግሎት | ትርፍ ለማግኘት | ድምር |
| ሀ. 1. አራት ባንኮች;. የሳይቤሪያ ፤ የንግድ የሩሲያ አለም አቀፋዊ እና የቅናሽ ባንክ | 413.7 | 859.1 | 1.272.8 |
| 2. ሁለት ባንኮች :.. ንግድና ኢንዱስ ትሪያዊ ፤ እና የሩሲያና እንግሊዝ | 239.3 | 169.1 | 408.4 |
| 3. አምስት ባንኮች :.. የሩሲያና እስያ ፤ ቅዱስ ፒተርስበርግ የግል አዞቮ ዶን ዩንየን—ሞስኮ ፤ የሩሲያና ፈረን ሣይ ንግድ | 711.8 | 661.2 | 1.373.0 |
| በድምሩ 11 ባንኮች ሀ/= | 1.364.8 | 1.689.4 | 3.054.2 |
| ለ. ስምንት ባንኮች ፥ የሞስኮ ነጋዴዎች ቮልጋ—ጀንከር እና ኩባንያው ፤ የቅዱስ ፒተርበርግ የንግድ (ጥንት ዌልበርግ) ፥ የሞስኮ ባንክ (ጥንት ሪያቡሽንስኪ )፤ ሞስኮ ቅናሽ ሞስኮ የንግድ ፥ ሞስኮ የግል /19 ባንኮች/ | 504.2 | 391.1 | 895.3 |
| ድምር | 1.869.2 | 2.080.5 | 3.949.5 |

ከነዚህ አሀዞች መረዳት እንደሚቻለው ፣ . . . «ለሥራ» ከሚውለው የትልልቅ ባንኮች ፣ በግምት አራት ቢሊዮን ሩብሎች ካፒታል ውስጥ ከሶስት—አራተኛው እጅ የሚበልጠው ፣ ከሶስት ቢሊዮን በላይ ፣ በትክክል የውጪ ባንኮች « ግልገል ኩባንያዎች » የሆኑ ባንኮች ፣ ይበል ጡንም የፓሪስ ባንኮች (ዝነኛ ሶስቱ ፣ ዩኒየን ፓሪሲየን ፣ ፓሪስ ኢት ፒይ — በና ሶስየቴ ዠኔራል) እና የበርሊን ባንኮች (በተለይም የዶች ባንክና ዲስከንቶ — ጊሰልሸ ፍት) ሐብት ነበር ። ከታላላቅ የሩሲያ ባንኮች መካከል ሁለቱ ፣ ራሺያን (የሩሲያ ባንክ ለውጪ ንግድ ) እና ኢን ተርናሽናል (ቅዱስ ፒተርስበርግ ኢንተርናሽናል ንግድ ባንክ ) « ሶስት አራተኛ የጀርመን ወረት በመጠቀም» በ1906 ና በ1912 መካከል ፣ ወረታቸውን ከ44,000,000 ወደ 98,000,000 ሩብል ፣ እና መጠባበቂያቸውን ከ15,000,000 ወደ 39,000,000 ሩብል ከፍ አድርገዋል ። የመጀመሪየው ባንክ የበርሊን ጀርመን ባንክ « ኮንሰርን» ንብረት ሲሆን ሁለተኛው ደግሞ የበርሊን ዲስኮንቶ — ጊስልሻፍት ንብረት ነው ። የተከበረው አግሀድ ፣ ይበልጡ አክሲዮኖች በጀርመን ባንኮች ለመያዛቸው ሐቅና ብሎም የሩሲያ ባለአክሲዮኖች አቅመቢስ ስለመሆናቸው ሐቅ ቁጭት ያሳያል ። በርግጥ ወረት ወደ ውጪ የሚል ከው ሀገር እፍታውን ያነሳል ። ለምሣሌ የበርሊን ጀር መን ባንክ ፣ የሳይቤርያን ንግድ ባንክ አክሲዮኖች በበ ርሊን ገበያ በማዋል ፣ ለአንድ ዓመት ያህል በፓርትፍሊ ዎው ውስጥ አቆይቶ ፣ ለ100 በ193 ተመን ማለትም ከመ ደበኛ ተመናቸው በሁለት እጥፍ በመሸጥ ሂልፈርዲንግ « የአሻሻጭ » ትርፎች ብሎ የሚጠራውን ፣ በግምት 6. 000,000 ሩብል የሚሆን ትርፍ አግኝቷል ።

የኛ ዶራሲ ፣ የዋናው የቅዱስ ፒተርስበርግን ባንኮች ጠቅላላ « ችሎታ » 8,235,000,000 ሩብሎች ወደ 8 1/4 ቢሊዮን አድርጎ ያስቀምጠዋል ። እናም « ይዞታዎቹ » ወይም የውጪ ባንኮች ያሳደሩባቸው ተጽዕኖ እስከምን እንደሆነ ቀጥሎ ባለው መልክ ያቀርባል ። የፈረንሣይ ባንክ 55 እጅ በመቶ ፣ የእንግሊዝ 10 እጅ በመቶ ፣ የጀርመን 35 እጅ በመቶ ። ከሚንቀሳቀሰው ጠቅላላ 8,235,000 ሩብል ወረት ፣ 3,687,000,000 ሩብል ወይም ከ40 እጅ ከመቶ በላይ የፕሮዲጎልና የፕሮዳሚት ሲንዲኬቶችና ዘይት ፣ ብረታብረትና የሲሚንቶ ኢንዱስትሪዎች ሲንዲኬቶች አክሲዮኖች ይዞታ ነው። ስለዚህ ፣ በካፒታሊስት ሞኖፖሊዎች መመሥረት ምክንያት የባንክና የኢንዱስትሪያዊ ወረት መዋሀድ በሩሲያ ከፍተኛ እርምጃ አድርጓል ።

በጥቂቶች እጅ የደለበውና ውስጥ ውስጡን ሞኖፖሊን የሚያራምደው ገንዘባዊ ወረት ከተትረፈረፉት ፣ ኩባንያዎች ከገንዘቦች መታተም ፣ ከመንግሥት ብድሮች ፤ ወዘተ . . . የሚመጣውን ሠፊና ከዚህ በፊት ታይቶ ያላታወቀ ትርፍን በማረጋገጥ ፣ የገንዘባዊ ሥልጣንን የበላይነትና በጠቅላላው ሕብረተሰብ ላይ ለሞኖፖሊስቶች ጥቅም ሲባል የሚጣለውን ተጨማሪ የአሥራት ክፍያ ያጠናክራል ። በሂልፈርዲንግ ከተጠቀሱት የአሜሪካ ትረስቶች የንግድ ሥራ ዘዴዎች አያሌ ምሳሌዎች መካከል አንድ እነሆ ። በ1887 ሀቭማየር ፣ ጠቅላላ ወረታቸው 6,500,000 ዶላርስ የሆነ ፣ አሥራ አምስት ትንንሽ ድርጅቶች በማዋሃድ የስኳር ትረስት አቋቁሞ በሚገባ « ውሃ የጠጣ » አሜሪካኖች እንደ ሚሉት ፣ የትረስቱ ወረት 50,000,000 ዶላር ነው ተብሎ ተነገረ ። ይህ « ከሆነው በላይ ካፒታልን ማሳደግ » ፣ ልክ የተባበ

ሩት አሜሪካ የዐረብ ብረት ኮርፖሬሽን በተቻለው መጠን በርካታ የብረት ማዕድን ጉድጓዶችን በመግዛት ስለሚያ ገኘው የሞኖፖሊ ትርፍ በቅድሚያ መገመት እንደሚ ችለው ሁሉ ፣ በቅድሚያ የሞኖፖሊ ትርፉን ይገምታል ። እንደ እውነቱ ከሆነ ፣ የስኳሩ ትረስት ፣ ሰባት እጥፍ ፣ ወይም ትረስቱ ሲመሠረት ሥራ ላይ በዋለው ወረት ላይ 70 እጅ በመቶ ፣ « ውሃ በጠጣ » ወረት 10 እጅ በመቶ ወለድ ለመክፈል የሚያስችል የዋጋ ተመን ያወጣል ። በ1909 ዓ. ም. የስኳሩ ትረስት ወረት ወደ 90,000,000 ዶላር አደገ ። በሃያ ሁለት ዓመታት ውስጥ ወረቱን በአ ሥር እጥፍ አሳድጎ ነበር ።

በፈረንሳይ « የገንዘባዊ ሥልጣን » የበላይነት (በፈረ ንሣይ ገንዘባዊ ሥልጣንን በመቃወም ፣ አምስተኛው እትሙ በ1908 የወጣው የታወቀው የሊሲስ መጽሐፍ አርዕስት) ትንሽ ለየት ያለ መልክ ነበረው ። በጣም ኃያላን ከሆኑት ባንኮች መካከል አራቱ ሰነዶችን ከማተም ፣ አንጻራዊ ሳይሆን « በፍጹም ሞኖፖሊ » ይጠቀሙ ነበር ። በእውነታው ይህ « የትልልቅ ባንኮች ትረስት » ነው ። ሞኖፖሊ ደግሞ ከሚታይለው ሰነድ ሞኖ ፖሊስት ትርፍ መገኘቱን ያረጋግጣል ። አብዛኛውን ተበ ዳሪው ሀገር የብድሩን 90 እጅ በመቶ ብቻ ሲወስድ የቀ ረው 10 እጅ በመቶ ለባንኮችና ለአቀባባዮች ገቢ ይሆናል። ባንኮች ፣ ከ400,000,000 ፍራንክ ከሩሲያና ቻይና ብድር 8እጅ በመቶ ፣ ከ800,000,000 ፍራንክ ለሩሲያውያን የተሰጠ (1904) ብድር 10 እጅ በመቶ ፣ እና ከ62,000,000 ፍራ ንክ ለሞሮኮ ከተሰጠ ብድር (1904) 18.75 እጅ በመቶ ትርፍ አግኝተዋል ። ዕድገቱን ፣ በንዑስ የአራጣ ብድር ወረቱን ፣ የጀመረው ካፒታሊዝም በከፍተኛ የአራጣ ብድር ዕድገቱን ያበቃል ። « ፈረንሣዮች » ይላል ሊሲስ

የአውሮፓ የአራጣ አበዳሪዎች ናቸው» «የኤኮኖሚ ያዊ ኑሮ ሁኔታዎች በመላ ፣ በካፒታሊዝም መለዋወጥ ምክንያት እየተለዋወጡ ናቸው ። ከቋሚ ኅብረተሰብ ፣ ቋሚ ኢንዱስትሪ ፣ ንግድና መርከቦች ጋር « ሀገሪቱ » በአራጣ ሀብታም ትሆናለች ። » 8,000,000 ፍራንክ ወረት ያላቸው አምሣ ሰዎች ፣ በአራት ባንኮች ውስጥ የተከማቸ 2,000,000,000 ፍራንክ ለመቆጣጠር ይችላሉ ። የምናውቀው « የመያዣ ሥርዓትም » ወደ ተመሳሳይ ውጤት ይመራል ። ከታላላቆቹ ባንኮች አንዱ ፣ ሶስየቴ ዠኔራል ፣ ለምሣሌ ፣ 64,000 ሰነዶች ለግሌግል ኩባንያው » ለግብጹ የስኳር ማጣሪያ ፣ አድሏል ። ሠነ ዶቹ የታደሉት በ150 እጅ በመቶ ፣ ማለትም ባንኩ በአ ንድ ፍራንክ 50 ሣንቲም እንደሚያገኝ ተደርጎ ነው ። የአዲሱ ባንክ ድርሻዎች ልብወለድ ሆነው በመገኘታ ቸው « ሕዝቡም » ከ90 እስከ 100 ሚሊዮን ፍራንክ አጣ ። « ከሶስየቴ ዠኔራል ዳይሬክተሮች አንዱ የስኳር ማጣሪያ ዎቹ የዳይሬክተሮች ቦርድ አባል ነበር ። » ደራሲው ፣ «የፈረንሣይ ሪፑብሊክ የገንዘባዊ ንጉሥ ነች » « ሙሉ በሙሉ የገንዘባዊ ሥልጣን የበላይ ነች ፣ ገንዘባዊ ሥል ጣን በጋዜጣው በአስተዳደሩ ላይ ተጽዕኖ ያደርጋልና » ብሎ ቢደመድም የሚያስደንቅ አይደለም[53] ።

የገንዘባዊ ወረት ዋና ተግባር ከሆነው ፣ መተማመኛዎ ችን (ሴኩሪቲስ) ከማደል የሚገኘው ከመጠን በላይ የሆነው ትርፍ ፣ የገንዘባዊ ሥልጣን መዳበርና መጠናከር በጣም ጠቃሚ ሚና ይጫወታል ። « በግምት ለውጪ ብድር በመስጠት የሚገኘውን ትርፍ ያህል የሚያስገኝ አንድም የሀገር ውስጥ የንግድ ሥራ የለም » ይላል የጀርመን ማጋ ዚን ዳይ ባንክ[54] ።

«ምንም የባንክ ሥራ ፣ መተማመኛዎችን በማደል ከሚገኘው ትርፍ ጋር የሚወዳደር ትርፍ፣ አያስገኝም።» በጀርመን ኤኮኖሚስት መሠረት ኢንዱስትሪያዊ ሰነድ በማደል የሚገኘው መካከለኛ የዓመት ትርፍ የሚከተለው ነው ።

| | እጅ ከመቶ | | እጅ ከመቶ |
|---|---|---|---|
| 1895 . . | 38.6 | 1898 . . | 67.7 |
| 1896 . . | 36.1 | 1899 . . . . | 66.9 |
| 1897 . . | 66.7 | 1900 . . . . | 55.2 |

« ከ1891 እስከ 1900 ባለው አሥር ዓመት ፣ የጀርመን ኢንዱስትሪያዊ ሰነድን በማደል ከአንድ ሚሊዮን ማርክ የበለጠ ተገኝቷል ።[59] »

በኢንዱስትሪያዊ ንረት ጊዜ ፣ የገንዘባዊ ወረት ትርፍ ከፍተኛ ይሆናል ፣ በሚአዘቅጥበት ጊዜ ግን ትንንሽና ደካማ የንግድ ሥራዎች እስተኀአካቴው ይጠፋሉ ፣ ታላላቅ ባንኮች ከነሱ « ይዞታዎች » እነሱን በመግዛት ያገኛሉ ወይም እነሱን « መልሶ ከማቋቋምና» « ከማደራጀት » ለሚገኘው ትርፍ ይሳተፋሉ ። በኪሣራ የሚንቀሳቀሱትን ድርጅቶች « መልሶ በማቋቋሙ . . . በአክሲዮን የተገኘው ወረት ይመዘገባል ማለትም ትርፎች በትንሽ ወረት መሠረት ይከፋፈላሉ ፣ እናም በዚሁ ትንሽ ወረት መሠረት መተመናቸውን ይቀጥላሉ ። ወይም ገቢው ወደ ምንም ከወረደ ፣ ተጨማሪ ፣ ከቀድሞውና አነስተኛ ጥቅም ከሚያስገኘው ወረት ጋር በመጨመር ጠቃሚ ውጤት የሚያገኝ ፣ ወረት ይሠበሠባል ። « በነገራችን ላይ » ይላል ሂለፈርዲንግ በማከል «እነዚህ ሁለት መልሶ ማደራጀትና ማቋቋም ፣ ለባን

ኮች ፣ ድርብ ትርጉም አላቸው ። በመጀመሪያ ደረጃ እንደ ትርፍ አምጪ የንግድ ሥራ ፣ ሁለተኛ ደግሞ ፣ ችግር የደ ረሰባቸውን ኩባንያዎች የመቆጣጠሪያ ዕድል እንደማግ ኘት » ይላል[56] ።

ይህን ሁናቴ የሚገልጽ አንድ ምሳሌ እና ቅርብ ፡ የዶርት መንድ ዩኒየን የማዕድን ቁፈራ ኩባንያ በ1872 ዓ. ም. ተቋቋመ ። ወደ 40,000,000 ማርክ የሚደርስ የአክሲዮን ወረት ከታደለና ኩባንያው ለመጀመሪያው ዓመት የ12 እጅ በመቶ ወለድ ከከፈለ በኋላ ፣ የአክ ሲዮኖች የገበያ ተመን ወደ 170 ከፍ አለ ። የገንዘባዊ ወረት እፍታውን አነሳ ፣ ወደ 28,000,000 ማርክ የሚ ጠጋ ትንሽ ገንዘብ አገኘ ። የዚህ ኩባንያ ዋና የበላይ ተቆ ጣጣሪ የነበረው ፣ ወረቱን 300,000,000 ማርክ አድርሶ የነበረው ትልቁ የጀርመን ዲስኮንቶ ጊሲልሻፍት ነበር። ወደኋላ ላይ የኩባንያው የወለድ ክፍያ ወደ ምንም ወረደ ፣ እና ባለአክሲዮኖቹም ወረታቸውን « አሣንሰው ለመ ጻፍ » ፈቃደኛ ሆኑ ፣ ማለትም ፣ ሁሉንም ከማጣት ትንሽ ማጣትን መረጡ ። በተከታታይ በተደረገ « መልሶ ማቋ ቋም ፣ » በሠላሣ ዓመታት ጊዜ ውስጥ ከ73,000,000 ማርክ በላይ ከሕብረቱ መዝገብ ተሠርዞ ወጣ[2] » « በአሁኑ ጊዜ ፣ የኩባንያው የቀድሞ ባለአክሲዮኖች ፣ ከመዘገቡት የአክሲዮኖቻቸው ተመን 5 እጅ ከመቶ ብቻ ነው ያላ ቸው[57] ።» ይሁን እንጂ ባንኮቹ ከእያንዳንዱ መልሶ ማቋ ቋም » ጥቂት አግኝተዋል ። »

በፍጥነት በሚያድጉ ታላላቅ ከተሞች አካባቢ የሚገኝ መሬት የመግዛትንና [illegible]ስ በትርፍ የመሸጥን ሥራ ፣ የገንዘባዊ ወረት [illegible] [illegible]ታጊ ሥራ ሆና አግኝቶታል ። እዚ[illegible]ች ሞኖፖሊ

ከመሬት ኪራይ ሞኖፖሊና ከመገናኛ ዘዴዎች ሞኖፖሊ ጋር ይዋሃዳል ። ምክንያቱም የመሬት ተመኑ መወደድና እየቆራረጡ መልሶ የመሸጡ ዕድል፤ ወዘተ . . . በይበልጥ የሚወሠነው በከተማው መካከል ባለው አመቺ የመገናኛ ዘዴ ስለነበር ነው ። በተጨማሪም እነዚህ የመገናኛ ዘዴዎች ፣ ከሚመለከታቸው ባንኮች ጋር በመያዣ ሥርዓትና በቦታ ማከፋፈል በተዛመዱ ትልልቅ ኩባንያዎች ይዞታ ሥር ናቸው ። በውጤቱም ፣ የጀርመኑ ጸሐፊ ፣ ለዳይ ባንክ መጽሔት ዜና አቅራቢ የነበረው ስለመሬት ኅብትና ለአበዳሪ ስለሚሠጡ መያዣዎች ፣ ወዘተ . . . . . ልዩ ጥናት ያደረገው ኤል. ኤሽ ዊግ ፡ «የቀለዘ መሬት » (አመቺ የሆነ) ብሎ የሚጠራውን እናገኛለን ። መላ ቅጥ ያጣ ፣ በከተሞች አከባቢ የሚገኙ ለሕንጻ መሥሪያ የሚሆኑ ቦታዎችን ገዝቶ በትርፍ ለመሸጥ የሚደረግ ፍላጐት የሕንጻ ሥራ ድርጅቶች መውደቅ በጠንካራው የጀርመን ባንክ እርዳታ እስከ 100,000,000 ማርክ የሚደርስ ገንዘብ ሲሰበስብ የነበረው የጀርመኑ ቦሳው እና ክኖር ተቋም የደረሰበትን ውድቀት አይነት ፣ ዶች ባንክ እንኳን በመያዣ ሥርዓት በሠውር ፣ ከበስተጀርባ ፣ በመጠቀም 12,000,000 ማርክ ብቻ በመክሰር ከጉዳዩ ወጥቷል ፣ ከዚያም በኋላ ከልብ ወለዱ የሕንጻ ድርጅት ምንም ያላገኙት ትናንሽ ባለንብረቶች ፣ የሕንጻ መሥሪያ ቦታ ጨረታዎችን ፣ የሕንጻ ሥራ ፈቃድ፤ ወዘተ ወዘተ . . . ለመቆጣጠር ከ « ሐቀኛው » የጀርመን ፖሊስና አስተዳደር ጋር የተጭበረበረ ስምምነት የሚያደርጉት ፣ አሠሪዎችና ሠራተኞች መውደቅ ታይቷል[58] ።

የአውሮፓ ፕሮፌሰሮችና ደህና አመለካከት ያላቸው ቡርዣዎች በመመጻደቅ የሚያወግዙት « የአሜሪካ የሞራል ሕግጋት ወይም ሣይንስ ፣ » በገንዘባዊ ወረት ዘመን

በየሐገሩ የእያንዳንዱ ታላላቅ ከተማ የሞራል ሕግጋት ሆነዋል ።

በ1914 ዓ. ም. መጀመሪያ ላይ ፥ « የመጓጓዣ ትረስት » ለማቋቋም ማለትም ፥ በሶስቱ የበርሊን የመጓጓዣ ድርጅቶች የከተማው የኤሌክትሪክ ባቡር ፥ የትራምዌይ ኩባንያና የአውቶቡስ ኩባንያ መካከል « የጥቅሞች አካል» ለመመሥረት በርሊን ውስጥ ንግግር ይካሄድ ነበር ። « የአውቶብሱ ኩባንያ አክሲዮኖች ይበልጡ እጅ በሌሎቹ ሁለቱ የመጓጓዣ ኩባንያዎች እጅ የገባ መሆኑ ቀደም ብሎ የታወቀ ስለሆነ ፥ ይህ እቅድ መጀመሪያውኑ የታሰበበት መሆኑን አውቀነዋል ።» ይላል ዳይ ባንክ ሲጽፍ ። « ይህን ዓላማ የሚያራምዱት ፥ የመገናኛ አገልግሎቶችን በማዋሀድ ከፊሉ በተፈለገ ጊዜ ለሕዝብ አገልግሎት ሊውሉ ለሚችሉ ምጣኔ—ሀብቶች ጥንቃቄ ያደርጋሉ ፥ ብለው ሲሉ ሙሉ በሙሉ እናምናቸው ይሆናል ። ይሁን እንጂ ፥ ከሚመሠረተው የመጓጓዣ ትረስት በስተጀርባ ከፈለጉ ለመሬት ሐብት ንግዳቸው ጥቅሞች ሲሉ በሞኖፖሊ እንዲጠቃለሉ ያደረጓቸውን የመጓጓዣ ዘዴዎች ፥ በቁጥጥራቸው ሥር ሊያውሉ የሚችሉ ባንኮች ስላሉ ጥያቄው የተሳሰበ ይሆናል ። ስለእንዲህ ዓይነቱ ግምታዊ አሠራር ቁም ነገርነት አምኖ ለመቀበል ፥ የኤሌክትሪክ የባቡር ኩባንያን መመሥረት የገፋፉት የባንክ ጥቅሞች ፥ ኩባንያው ሲመሠረት ተከፍለው እንደነበር ማስታወሱ ይበቃል ። ይህም ማለት ፥ የዚህ የመጓጓዣ ድርጅት ጥቅሞች ከመሬት ንብረት ጥቅሞች ጋር የተያያዙ ናቸው ። ዋናው ነገር ፥ የዚህ ባቡር መሥመር የምሥራቁ ሐዲድ ፥ የሐዲዱ መዘርጋት ከተረጋገጠ ፥ ባንኩ ለራሱና የንግዱ ልውውጦች ተባባሪ ለሆኑ ለብዙዎቹ ይህ ነው የማይባል ትርፍ በማግኘት በሚሸጠው መሬት ላይ መነጣፍ ነበረበት ። »

አንድ ሞኖፖሊ ፣ አንድ ጊዜ ከተመሠረተና በሺህና በሚሊዮን የሚቆጠር ወረት መቆጣጠር ከጀመረ በመንግሥት አቋምና በሌሎች « ዝርዝር ሁኔታዎች » ሳይገታ ፣ በሕዝቡ ኑሮ በሁሉም አካባቢ ዘልቆ እንደሚገባ ጥርጥር የለውም ። በጀርመን የምጣኔ—ሀብታዊ ሥነ ጽሑፍ ውስጥ ስለ ፕሩሲያን ቢሮክራሲ ሐቀኛነት የሚነገር የተገነዘነት ምሥጋና ፣ እና ስለፈረንሣይ ፓናማ ውዝግብና ስለአሜሪካ የፖለቲካዊ መበስበስ በተዘዋዋሪ መንገድ መጥቀስ ፣ ማንበብ የተለመደ ነው ። ሐቁ ግን ፣ ለጀርመን የባንክ ጉዳዮች ታጥቀው የቆሙ የቡርዧ ሥነ ጽሑፎች እንኳን በየጊዜው ስለባንክ ሥራ ብቻ ከመጻፍ አልፈው፣ለምሳሌ፤ እየጨመረ የሚሄደውን የተደጋገመ የሕዝብ ባለሥልጣኖች በባንኮች መቀጠር አስመልክቶ « ስለባንኮች አስገምግርነት » ሲናገሩ ፣ በልቡ የበሀሬንስትራስን ገራገር ሥራ የሚመኘውስ የመንግሥት ባለሥልጣን ሐቀኛነት እንዴት ነው ? » ይላሉ[60]። (በሀራንስትራስ የጀርመን ባንክ ጠቅላይ መምሪያ የሚገኝበት የበርሊን ጐዳና ነው ።) በ1909 ዓ. ም. ፣ የዳይ ባንክ አታሚ ፣ አልፍሬድ ላንስበርግ ፣ እግረ መንገዱን ስለ ዊልሂለም የፍልስጤም ጉብኝት ፣ የጉዞውም ፈጣን ውጤት ያ አደገኛ « የጀርመን ተቋም ታላቅ የሥራ ውጤት ፣ የኛ የፖለቲካ አሻጥሮች ተደምረው ሊሆኑ የማይችሉትን የበለጠ ለመከበቡ » ምክንያት የሆነው የባግዳድ የባቡር መሥመር መዘርጋት መሆኑን የጻፈበትን « የባዘንታይን ምጣኔ—ሀብታዊ ጥቅም » የተሰኘ ጽሑፍ ጽፎ ነበር ። መከበብ የሚለው ቃል ፣ ኤድዋርድ ጀርመንን በመነጠል በኢምፔሪያሊስት ጸረ — ጀርመን አንድነት እንድትከበብ ያወጣውን ፖሊሲ ፣ የሚያመለክት ነው[61]። በ1911 ዓ. ም. ቀደም ሲል የጠቀስነውና ለዚሁ መጽሔት ዜና አቅራቢ የነበረው ፣ ኤሽዋግ ፣ ፕሉቶክራሲና (ባለጸጋና ኃይል መደብ) ቢሮክራሲ በሚል

ርዕስ አንድ ጽሑፍ ጽፎ ነበር ። በዚሁ ጽሑፍ ውስጥ ፣ ለምሣሌ ፣ ቮልኩር የሚባል ብርቱ ስሜት የነበረው የካርቴል ኰሚቴ አባል ፣ በመጨረሻም እንደተረጋገጠው ፣ በትልቁ ካርቴል ማለትም በዐረብ ብረት ሲንዲኬት ይህ ገቢ የሚያስገኝ ሥልጣን ተሰጥቶት የነበረ የጀርመን ባለ ሥልጣንን አጋልጦ ጽፎ ነበር ። ተመሳሳይ ጉዳዮች ፣ ሳይታሰብም ቢሆን ይህን የቡርዧ ደ.ራሲ ፣ በጀርመን ሕገ መንግሥት የተፈቀደው የምጣኔ — ሀብታዊ ነጻነት በብዙ የምጣኔ—ሀብት የንግድ ቅርንጫፎች ዘንድ ትርጉም የለሽ ሀረግ ይሆናል ፤ እናም አሁን ባለው የፕሎቶክራሲ (በሀብታሞች መደብ የሚመራ የሀብታሞች አስተዳደር) አመራር ፣ « ሠፊው ፖለቲካዊ ነጻነት እንኳን ፣ ነጻ ወደ አልሆነ ሕዝብ ብሔርነት ከመለወጥ አያድነንም» ብሎ እንዲያምን አስገድዶታል[62] ።

እንደሩሲያ ከሆነ ፣ አንድ ምሣሌ ማቅረብ ይበቃናል ። ከጥቂት አመታት በፊት የግምጃ ቤቱ (የገንዘብ) የብድር ክፍል ዳይሬክተር ፣ ዳቪዶቭ ፣ በአንድ ትልቅ ባንክ ውስጥ ለመቀጠርና በኮንትራቱ መሠረት በብዙ ዓመታት ጊዜ ውስጥ ከአንድ ሚሊዮን ሩብሎች በላይ ደመዝ ሊከፈለው ፣ ከሥልጣኑ በገዛ ፈቃዱ ተሰናብቶ እንደነበር ሁሉም ጋዜጦች አውርተው ነበር ። የብድሩ ፣ ክፍል ፣ ሥራው « የሁሉንም የሀገሪቱን የብድር ተቋሞች ተግባራት ማስተባበር » እና በፒተርስበርግና በሞስኮ ላሉ ባንኮች ከ800 እስከ 1000 ሚሊዮን ሩብልስ የንግድ ድርጅቶችን ለመርዳት ከመንግሥት የሚሠጠውን ገንዘብ መፍቀድ ፣ የሆነ አንድ ተቋም ነው[63]** ። የወረት ባለቤትነት ፣ ወረትን ለምርት አገልግሎት ከማዋል መለየት ፣ የብርን ወረት ከኢንዱስትሪያዊና ከእምራች ወረት መለየት ፣ እና ኑሮውን ሙሉ በሙሉ

ከገንዘብ ወረት በሚገኝ ገቢ ላይ የመሠረተውን አከራይ ከሥራ መሪውና የወረቱ አስተዳደር በቀጥታ ከሚመለከ ታቸው ሁሉ መለየት በአጠቃላይ የካፒታሊዝም ጠባይ ነው ። ኢምፔሪያሊዝም ወይም የገንዘባዊ ወረት የበላይነት፤ ይህ መለያየት ከፍተኛ መጠን የሚደርስበት ፣ ያ የካፒታ ሊዝም ከፍተኛ የዕድገት ደረጃ ነው ። የገንዘባዊ ወረት ከሌሎች የወረት ዓይነቶች ሁሉ በላይ መሆን ማለት ፣ የአከራይና የገንዘባዊ ሥልጣን ወሳኝ ኃይል መሆን ጥቂት በገንዘብ በኩል « ሃያላን » የሆኑ መንግሥታትን ከሌሎች ውስጥ ነጥሎ ማውጣት ማለት ነው ። ይህ ሂደት በምን ደረጃ ላይ እንዳለ ለመገመት በማሠራጨት ማለትም ማና ቸውንም ዓይነት መተማመኛ በማደል ላይ የቀረበውን ስታቲስቲክስ መመልከት ይበቃል ።

በዓለም አቀፍ የስታቲስቲክስ ተቋም ጋዜጣ ውስጥ ኤ ኒ ይማርክ ሲጽፍ***64 በከፊልም ቢሆን በምጣኔ— ሀብታዊ ሥነጽሑፍ ውስጥ የተጠቀሰውን ፣ መተማመኛ ዎችን በአለም ዙሪያ ማሠራጨትን አስመልክቶ ፣ በጣም አጠቃላይ የሆኑ ፣ የተሟሉና ተነጻጻሪ የሆኑ አሐዞችን አሳትሞ ነበር ። ቀጥሎ የተመለከቱት ያቀረባቸው ለአ ርባ ዓመታት የተከናወኑ ጠቅላላ አሐዞች ናቸው ።

ጠቅላላ የታደሉ በቢሊዮን ፍራክ
(በአሥር አመታት)

| | |
|---|---|
| 1871—1880 | 76.1 |
| 1881—1890 | 64.5 |
| 1891—1900 | 100.4 |
| 1901—1910 | 197.8 |

በ1870ዎች ውስጥ በተለይም ከፈረንሳይና ጀርመን ጦርነት ጋር ተያይዞ በተሰጡት ብድሮችና ከጦርነት በኋላ በጀርመን ኩባንያ አሳዳጊ ንረት በመጀመሩ ለጠቅላላው

ዓለም የታደለው መጠን ከፍተኛ ነበር ። በጠቅላላው ፣ በሶስቱ የአሥራ ዘጠነኛው ምዕተ ዓመት መጨረሻ የአሥር ዓመታት ጊዜዎች ውስጥ ጭማሪው ይህንንም ያህል ፈጣን ሳይሆን ፣ በመጀመሪያው የሃያኛው ምዕተ ዓመት የአሥር ዓመት ጊዜ ወደ 100 እጅ የሚደርስ ከፍተኛ እንቅሥቃሴ ታይቷል ። ስለሆነም ፣ የሃያኛው ምዕተ ዓመት መጀመሪያ ቀደም ብለን ያነሳናቸውን የሞኖፖሊዎች (ካርቲሎች ፣ ሲንዲኪቶች ፣ ትረስቶች) እድገት በሚመለከት ብቻ ሳይሆን የፊናንስ ወረት ዕድገትንም በሚመለከት ቀውስ የታየበት ወቅት ነበር ።

ጠቅላላ የታደሉት መተማመኛዎች መጠን በአሁኑ ጊዜ ፣ በ1910 ፣ በግምት ወደ 815,000,000 ፍራንክ እንደሚሆን ኔይማርክ ይገምታል ። ከዚህ ድምር ላይ ፣ ተደጋጋሚ የሆኑትን መጠኖች በመቀነስ ፣ ጠቅላላውን በብዙ ሀገሮች መካከል ወደ ተከፋፈለው ከ575,000 እስከ 600,000 ቢሊዮን ፍራንክ ዝቅ ያደርገዋል ። (600,000 ሚሊዮንን በመውሰድ ዝርዝሩ እነሆ) ፤

በ1910 በመዘዋወር ላይ ያሉ ገንዝባዊ መተማመኛዎች ፤

(በቢሊዮን ፍራንክ)

| | | |
|---|---|---|
| ታላቋ ብሪታንያ | 142 | 479 |
| የተባበሩት አሜሪካ | 132 | |
| ፈረንሣይ | 110 | |
| ጀርመን | 95 | |
| ሩሲያ | 31 | |
| አውስትራሊያና—ሀንጋሪ | 24 | |
| ኢጣሊያ | 14 | |
| ጃፓን | 12 | |
| ሆላንድ | 12.5 | |

| | |
|---|---|
| ቤልጅየም . . . . . . . . . . . . | 7.5 |
| ስፔይን . . . . . . . . . . . . . | 7.5 |
| ስዊዘርላንድ . . . . . . . . . . . | 6.25 |
| ዴንማርክ . . . . . . . . . . . . | 3.75 |
| ሲዊድን ፣ ኖርዌይ ፣ ሩማንያ ፤ ወዘተ . . . | 2.5 |
| ድምር | 600 |

ከነዚህ አሐዞች ፣ በጣም ባለጸጎች ከሆኑት ሀገሮች ውስጥ አራቱን ፣ እያንዳንዳቸው በግምት ከ100 ሺ እስከ150 ሺ ሚሊዮን ፍራንክ የሚደርስ የመተማመኛዎች ይዞታ ያላ ቸውን ፣ አግጠው ወጥተው በአንድ ጊዜ እናያቸዋለን ። ከነዚህ ከአራቱ ፣ ሁለቱ ፣ እንግሊዝና ፈረንሣይ ፣ የጥንት ካፒታሊስት ሀገሮች ሲሆኑ ፣ ወደፊት እንደምናየው ይበ ልጥ ቅኝ ግዛቶች አሏቸው ፣ ሌሎቹ ሁለቱ ፣ የተባበሩት አሜሪካና ጀርመን ፣ የዕድገትን ፍጥነትንና በኢንዱስትሪ የሞኖፖሊዎች መስፋፋት መጠንን በሚመለከት ቀንደኛ የካፒታሊስት ሀገሮች ናቸው ። በአንድነት ፡ እነዚህ አራት ሀገሮች ፣ የአለምን የገንዘባዊ ወረት በግምት 80 እጅ ከመቶ የሚሆነው የ479,000,000 ፍራንክ ባለቤቶች ናቸው ። በዚህም ሆነ በዚያ ፣ ጠቅላላው ዓለም ከሞላ ጐ ደል ፣ የነዚህ ዓለም አቀፍ የባንክ ኃላፊ ሀገሮች ፣ የነዚህ አራት የአለም ገንዘባዊ ወረት « ምሰሶዎች » ተበዳሪና ገባር ሆኗል ።

ዓለም አቀፍ የጥገኝነት አሠራር መረብንና የገንዘባዊ ወረት ግንኙነቶችን በመፍጠር ረገድ በተለይ ወረትን ወደ ውጪ መላክ ምን ሚና እንደተጫወተ መመርመሩ ይጠቅማል ።

# ምዕራፍ አራት ፤

# የወረት ወደ ውጪ መላክ

ነጻ ውድድር ያልተከናፈለ የበላይነት ይዞ በነበረ በት ጊዜ የአሮጌው የካፒታሊዝም አይነተኛ ጠባይ የዕ ቃዎች ወደ ውጭ መላክ ነበር ። ሞኖፖሊዎች በገነኑበት ጊዜ ያለው የመጨረሻው ካፒታሊዝም ደረጃ አይነተኛ ጠባይ ደግሞ የወረት ወደ ውጪ መላክ ነው ።

ካፒታሊዝም ፣ የጉልበት ኃይል ራሱ ሸቀጥ የሆነበት የሸቀጥ ምርት ራሱ ከፍተኛ የዕድገት ደረጃ የደረሰበት ነው ። በሀገር ውስጥ የሚደረግ የሸቀጥ ልውውጥና በተ ለይም ዓለም አቀፋዊ የሸቀጥ ልውውጥ ዕድገት የካፒታ ሊዝም አይነተኛ ጠባይ ነው ። በካፒታሊስት ሥርአት ውስጥ ፣ የእያንዳንዱ ተቋም ፣ የኢንዱስትሪ ቅርንጫፎ ችና ሀገሮች ያልተስተካከለና የተኩመታተረ ዕድገት የማ ይቀር ሒደት ነው ። እንግሊዝ በአሥራ ዘጠነኛው ምዕተ ዓመት አጋማሽ ላይ የነጻ ንግድን ከሥራ ላይ በማዋልና ከማንኛውም ሀገር ቀድማ ካፒታሊስት በመሆን ፣ « የዓ ለም መደብር » ነኝ . . በለውጡ ጥሬ ዕቃ ለሚያቀርቡ ልኝ ሀገሮች ሁሉ የተፈበረኩ ዕቃዎችን የማቀርብ ነኝ ብላለች ። ይሁን እንጂ ይህ ሞኖፖሊ ፣ በመጨረሻው የአሥራ ዘጠኝ መቶ ምዕተ ዓመት እሩብ አካባቢ ፣ አሽ ቆለቆለ ፣ ምክንያቱም ሌሎች ሀገሮች በታሪፍ « ከለላ » አማ ካይነት ወደ ነጻ ካፒታሊስት መንግሥትነት ስላደጉ ነው ። በሃያኛው ምዕተ ዓመት መግቢያ ላይ አዲስ ዓይነት ሞና ፖሊ ተከስቶ እናያለን ። በመጀመሪያ ፣ የካፒታላዊ ዕድ ገት ደረጃን በተቀዳጁ አገሮች ውስጥ ሁሉ የሞኖፖሊስት ካፒታሊስት ማሕበራት መመሥረት ፤ ሁለተኛ ደግሞ ፣

የወረት መድለብ ግዙፍ መጠን የደረሰባቸው ጥቂት ሀብ ታም ሀገሮች ሞኖፖሊስት አቋም ናቸው ። በሠለጠኑት ሀገሮች ውስጥ ከፍተኛ « የወረት መትረፍረፍ » ዕድገት ታይቷል ።

ካፒታሊዝም ፣ በዛሬው ጊዜ ከኢንዱስትሪ በጣም ወደኋላ ቀር የሆነውን እርሻን በሁሉም ቦታ ቢያስፋፋ ኖሮ ፣ የቴክኒክ ዕድገት በአስደናቂ አኳኋን እየተስፋፋ ፣ በያለበት ከፊል ረሀብተኛ የሆነውንና ድህነት ላይ የወደ ቀውን የሠፊውን ሕዝብ የኑሮ ደረጃ ለማሳደግ ጥረት ቢያ ደርግ ኖሮ ፣ የወረት መትረፍረፍ ጥያቄ ቦታ ሊኖረው እን ደማይችል ይታወቃል ። ይኸ ካፒታሊዝምን « የሚነቅፉ» ንዑሥ—ከበርቴዎች የሚያራምዱት ሃሣብ ነው ። ነገር ግን ካፒታሊዝም እነዚህን ነገሮች ከፈጸመ ካፒታሊዝም ሊባል አይችልም ። ምክንያቱም ያልተስተካከለ ዕድገ ትም ሆን የሰፊው ሕዝብ በከፊል ረሀብተኛነት ደረጃ መኖር ፣ ሁለቱም የዚህ ሥልተምርት መሠረታዊና መሆን ያለባቸው ሁኔታዎችና መንሥኤዎች ናቸው ። ካፒታሊ ዝም አሁን ያለውን አቋሙን ይዞ እስከቆየ ድረስ፣የተትረ ፈረፈ ወረት ፣ በአንድ ሀገር ውስጥ ያለውን ሠፊ ሕዝብ የኑሮ ደረጃ ከፍ ለማድረግ ጥቅም ላይ በመዋል ፈንታ ፣ ይህን ማድረግ የካፒታሊስቶችን ትርፍ ይቀንሠዋልና ፣ ወረት በሥልጣኔ ኋላ ቀር ወደሆኑ ሀገሮች እየተላከ ትርፍን ለማካበት እንዲያገለግል ይደረጋል ። በነዚህ ባልሠለጠኑ ሀገሮች ውስጥ ትርፍ በሽበሽ ነው ፣ ምክንያቱም ወረት እንደልብ አይገኝም ፣ በአንጻራዊ አመለካከት የመሬት ተመን ርካሽ ነው ፣ ምንዳእ ዝቅተኛ ነው ፣ ጥሬ እቃም ርካሽ ነው ። ወረትን ወደውጭ የመላኩ ሁኔታ የሚፈጠ ረው ፣ ቁጥራቸው በርከት ያለ ያልሠለጠኑ ሀገሮች ወደ ዓለም አቀፍ የካፒታሊስት ግንኙነት ተሥበው እንዲገቡ

ስለተደረገ ነው ። በነዚህ ሀገሮች ውስጥ ዋና ዋና የባቡር መሥመሮች ተዘርግተዋል ወይንም እየተዘረጉ ናቸው ፤ ለኢንዱስትሪያዊ ዕድገት የሚያሥፈልጉት መሠረታዊ ሁኔታዎች ተፈጥረዋል ፤ ወዘተ . . ። የወረት ወደውጪ መላክ አስፈላጊነት የሚመጣው ፣ በጥቂት ሀገሮች ካፒታሊዝም « በጣም ከመብሰሉ » የተነሣና (እርሻ ኋላ ቀር በመሆኑና ሠፊው ሕዝብ ድህነት ላይ የወደቀ በመሆኑ) ወረት «ትርፍ» የሚሠጥበት የሥራ መስክ ስለማግኘቱ ነው ።

ከዚህ በታች ሶስት ዋና ዋና ሀገሮች ወደውጭ በመላክ ሥራ ላይ የዋሉትን ወረት ግምታዊ ተመን በመዘርዘር እናቀርባለን[65] ።

በውጪ ሀገር ወጪ የተደረገ ወረት (በቢሊዮን ፍራንክ) ፡—

| ዓመተ ምህረት | ታላቋ ብሪታንያ | ፈረንሣይ | ጀርመን |
|---|---|---|---|
| 1862 | 3.6 | — | — |
| 1872 | 15.0 | 10/1869/ | — |
| 1882 | 22.0 | 15/1880/ | ? |
| 1893 | 42.0 | 20/1890/ | ? |
| 1902 | 62.0 | 27—37 | 12.5 |
| 1914 | 75—100 | 60 | 44.0 |

ይህ ሠንጠረዥ ፣ የወረት ወደውጪ መላክ ከፍተኛ ደረጃ የደረሰው በሃያኛው ምዕተ ዓመት መግቢያ ላይ ብቻ መሆኑን ያሣያል ። ከጦርነቱ በፊት በሶስቱ ዋና ዋና ሀገሮች በውጪ ሀገር ሥራ ላይ የዋለው ወረት መጠን በ175, 000,000,000 እና በ200,000,000,000 ፍራንክ መካከል ይሆናል ። በመካከለኛ የ5 እጅ በመቶ ሒሣብ ከዚህ ድምር በዓመት የሚገኘው ገቢ ከ8ሺ እስከ 10ሺ ሚሊዮን ፍራ

ንክ ይደርሳል ። ይህ እንግዲህ ይበልጡ የዓለም ሀገሮችና ብሔሮች በኢምፔሪያሊስት ጭቆናና ብዝበዛ ሥር እንዲወድቁ ፣ ለጥቂት ባለጸጋ መንግሥታት ጥባቴነት ጠንካራ መሠረት ጥሏል ማለት ነው ።

ይህ በውጪ ሀገር ሥራ ላይ የዋለው ወረት ፣ በብዙዎቹ ሀገሮች መካከል እንዴት ነው የሚከፋፈለው ? የት ነው እንዲሠራ የተደረገው ? ለዚህ ጥያቄ ፣ ግምታዊ ፣ ግን በአሁኑ ጊዜ የኢምፔሪያሊዝም አንዳንድ አጠቃላይ ዝምድናዎችና ግንኙነቶች ላይ በቂ ብርሃን ሊፈነጥቅ የሚችል ፣ መልስ ብቻ ነው ሊሠጥ የሚችለው ።

ግምታዊ የውጪ ወረት ሥርጭት (1910 ገደማ) በተለያዩ የዓለም ክፍሎች ፡—

| አሕጉሮች | በሚሊዮን ማርክ | | | |
|---|---|---|---|---|
| | ታላቋ ብሪታንያ | ፈረንሣይ | ጀርመን | ድምር |
| አውሮፓ | 4 | 23 | 18 | 45 |
| አሜሪካ | 37 | 4 | 10 | 51 |
| እስያ ፣ አፍሪካና አውስትራሊያ | 29 | 8 | 7 | 44 |
| ድምር | 70 | 35 | 35 | 140 |

የእንግሊዝ ወረት ሥራ ላይ መዋያ አካባቢዎች ፣ እስያን ፣ ወዘተ ሳንጨምር ፣ በአሜሪካም ጭምር (ለምሣሌ ካናዳ) ሠፋፊ የሆኑት ቅኝ ግዛቶቿ ናቸው ። በዚህ በኩል በጣም በርካታ የወረት ወደውጪ ፣ መላክ ለኢምፔሪያሊዝም ስለሚሠጠው ጥቅም ወደፊት ከማብራራው ፣ ከሰፊ የቅኝ ግዛቶች መኖር ጋር ፣ በቅርብ የተሣሠረ ነው ። የፈረንሣይ ሁናቴ ግን ለየት ያለ ነው ። ወደውጪ የሚላከው የፈረንሣይ ወረት ይበልጡ በአውሮፓ ፣ በመጀመ

ሪያ ደረጃ በሩሲያ ( ቢያንስ አሥር ቢሊዮን ፍራንክ ) ነው ሥራ ላይ የሚውለው ። ይህም ይበልጡ የብድር ወረት ሲሆን ፣ ለኢንዱስትሪያዊ ተቋሞች ሳይሆን ለመንግሥት የሚበደር ነው ። እንደ እንግሊዝ የቅኝ ግዛት ኢምፔሪያ ሊዝም ሳይሆን ፣ የፈረንሳይ ኢምፔሪያሊዝም ፣ የአራጣ ኢምፔሪያሊዝም ተብሎ ሊጠራ ይችላል ። የጀርመንን ሁናቴ ያየን እንደሆን ሶስተኛ ዓይነት ሆኖ እናገኘዋለን ። ቅኝ ግዛቶች እምብዛም ናቸው ፣ እና ወደውጪ የሚላከው የጀርመን ወረት በአውሮፓና በአሜሪካ መካከል በተስተ ካከለ አኳኋን ይከፋፈላል ።

የወረት ወደውጭ መላክ ፣ ወረቱ የሚሔድላቸውን ሀገሮች የካፒታሊዝም ዕድገት ተፅዕኖ ከማሳደሩም በላይ በከፍተኛ ደረጃ ያፋጥነዋል ። የወረት ወደውጭ መላክ ፣ በተወሠነ መጠንም ቢሆን የላኪውን ሀገር ዕድገት የሚ ያንቅ ቢሆንም ፣ ይህን የሚያደርገውም በዓለም ዙሪያ የካፒታሊዝም ዕድገት ሥር እንዲሠድና እንዲስፋፋ በማ ድረግ ነው ።

ወረት ላኪ ሀገሮች ሁል ጊዜ አንዳንድ « ጥቅሞችን» ለማግኘት ይችላሉ ፤ የነዚህም ጥቅሞች ባህሪ ለገንዘ ባዊ ወረትና ሞኖፖሊ የታሪክ ወቅት ልዩነት አንድ ብር ሃን ይፈነጥቃል ። የሚከተለው ሐተታ ፣ ለምሳሌ ፣ በ19 13 ዓ. ም. ወጥቶ በነበረው ፣ በዳይ ባንክ በርሊን መጽ ሔት ውስጥ ሠፍሮ የነበረ ነው ።

« የአሪስቶፌንን ብርዕ ለማስነሣት የቻለው ኰሜ ዲ (የሕይወትን ብሩህ ክፍል የሚያቀርብ ትርኢት ) ፤ ከቅርብ ጊዜ ወዲህ ፣ ስለዓለም አቀፍ የወረት ገበያ በመ ቅረብ ላይ ያለው ነው ። አያሌ የውጪ ሀገራት ፣ ከእስፔይን እስከ ባልካን መንግሥታት ፣ ከሩሲያ እስከ አርጀንቲና ፣ ብራዚልና ቻይና ፣ በግልጽ ወይንም በድብቅ ፣ ለብድር ፣ አንዳንድ ጊዜ ከጠበቀ ፍላጐት ጋር ወደትልቁ የገንዘብ

ገበያ እየመጡ ናቸው ። ለጊዜው የገንዘቡ ገበያ ብሩህ አይደለም ፣ የፖለቲካ አመለካከቱም ተስፋ ያለው አይ ደለም ። አንድም የገንዘብ ገበያ የወጪ ብድር ሲጠየቅ እምቢ ያለ የለም ፣ ምክንያቱም አንድ ጐረቤቱ በአጋጣ ሚው ይጠቀምና ብድሩን በመሥጠት በአጸፋው ሊያገኝ የሚችለውን ጥቅም ሊወስድበት ስለሚችል በነዚህ ዓለም አቀፋዊ የንግድ ስምምነቶች ሁል ጊዜ ተጨማሪ ጥቅሞ ችን ለማግኘት ዕድል ያገኛል ፣ ለምሳሌ በንግድ ስምምነት ለሱ የሚስማሙ ሐረጐችን መምረጥ ፣ የከሰል ጣቢያ ማግ ኘት ፣ ወደብ ለመሥራት መዋዋል ፣ በመንግሥት የሚ ሠጥ ሙብት ወይንም የጦር መሣሪያ ጥያቄ ማግኘትና የመ ሣሠሉትን[66] »

ገንዘባዊ ወረት የሞኖፖሊዎችን ከፍተኛ የታሪክ ወቅት አመጣ ፣ ሞኖፖሊዎች በበኩላቸው በያሉበት የሞ ኖፖሊስትን መርሐ ግብር ፤ ያስተዋውቃሉ ፤ « ግንኙነ ቶችን » ትርፍ ለሚያስገኝ የንግድ ስምምነት ማዋል በነጻ ገበያ ውድድር ቦታ ተተካ ። አንዱ ሁልጊዜ የሚደረ ገው ነገር ደግሞ በብድር ከሚገኘው ገንዘብ ከፊሉን በአበዳሪው ሀገር ዕቃዎችን ፣ በተለይም የጦር መሣሪያ ዎች ፣ ወይንም መርከቦች ፤ ወዘተ.. ለመግዣ እንዲውል ቃል ማስገባት ነው ። ባለፉት ሁለት የአሥር ዓመታት ጊዜ ውስጥ (1890—1910) ፈረንሣይ በዚህ ዘዴ ወደመ ጠቀሙ አዘንብላ ነበር ። ስለዚህ ፣ የወረት ወደውጪ መላክ የሸቀጦችንም መላክ ያበረታታል ። በዚህ ሁኔታ በሁለት በተለይ ትልልቅ በሆኑ ተቋሞች መካከል የሚደ ረገው የንግድ ሥራ ፣ ሺልደር[67] «ለዘብ» . . . ባለ አኳኋን እንደገለጸው ፣ « ለመበስበስ ዳር ዳር እያለ ነው ። » ክሩፕ በጀርመን ፣ ሽነይደር በፈረንሣይ ፣ አርምስትሮንግ በእን ግሊዝ ከታላላቅ ባንኮችና መንግሥታት ጋር ግንኙነት ያላቸው ፣ ብድር በሚታቀድበት ጊዜ « ተንቀው » ሊቀሩ

የማይችሉ ፣ የትልልቅ ተቋሞች ምሣሌዎች ናቸው ።

ፈረንሣይ ፣ ለሩሲያ ብድር በሠጠችበት ጊዜ ፣ የመ ከረም 16/1905 ዓ. ም·ቱን ፣ እስከ 1917 የንግድ ግንኙነቱ እንዲቀጥል ፣ ለአንዳንድ መብቶች ቃል ያስገባቻትን የንግድ ውል ባደረገችበት ጊዜ ፣ « አስጨንቃ » ይዛት ነበር ። የፈረንሳይና ጃፓን የንግድ ውል በተደረገበት በነሐሴ 19 ቀን 1911 ዓ. ም. ተመሣሣይ ነገር ፈጽማለች ። ከ1906 እስከ 1911 ዓ.ም. ለሰባት ወራት ብቻ በመሐሉ ተቋርጦ ፣ ፀቆየው በሰርቢያና በአውስትሪያ መካከል የነበረው የታሪፍ (ከውጭ በሚመጡ ዕቃዎች ላይ ተጨማሪ ግብር) ጦርነት ፣ የተቀሠቀሰው በከፊልም ቢሆን ፣ ለሰር ቢያ የጦር መሣሪያዎች ለማቅረብ ፈረንሣይና አውስትሪያ አድርገው በነበረው ውድድር ነው ። በጥር 1912 ዓ. ም. ፖል ዴሻኔል ፣ በሕግ መምሪያ ምክር ቤት ከ1908 እስከ 1911 ዓ. ም. የፈረንሣይ ተቋሞች ለሰርቢያ ያቀረቡዋ ቸው የጦር መሣሪያዎች ግምት ወደ 45,000,000 ፍራንክ እንደሚደርስ ገልጧል ።

ሳኦፖሎ (ብራዚል) ከሚገኘው የአውስትርያና ሀንጋሪ ቆንሲል የተገኘው ዘገባ እንዲህ ይላል ፣ « የብራዚል የባ ቡር ሐዲድ መሥመር የመዘርጋት ሥራ የሚካሔደው በይበልጥ በፈረንሣይ ፣ በቤልጅግ ፣ በእንግሊዝና በጀር መን ወረት ነው ። ከነዚህ የባቡር መሥመሮች መዘር ጋት ጋር በተያያዘው የገንዘባዊ አሠራር የሚመለከታቸው ሀገሮች ለዚሁ ሥራ የሚያስፈልጉትን ቁሣቁሶች ከነሱ እንዲገዙ ቃል ያስገባሉ ። »

ይህ ገንዘባዊ ወረት በግልጽ መረቡን በመላው ዓለም እንደሚዘረጋ ማንም ሊናገር ይችላል ። በዚህ መንገድ ዓይነተኛ ሚና የሚጫወቱት በቅኝ ግዛቶች የተቋቋሙት ባንኮችና ቅርንጫፎቻቸው ናቸው ። በዚህ በኩል « ጥሩ ዕድል» የገጠማቸውን « የቀድሞ » ቅኝ ገዢዎች ፣ የጀር

መን ኢምፕሪያሊስቶች በቅናት ዓይን ነው የሚመለከ ቷቸው ። በ1904 ዓ. ም. ታላቋ ብሪታንያ 50 የቅኝ ግዛት ባንኮች ከ2,279 ቅርንጫፎች ጋራ (በ1910 ተራ ባን ኮች ከ5,449 ቅርንጫፎች ጋር) ፈረንሣይ 20 ባንኮች ከ136 ቅርንጫፎች ፤ ሆላንድ 16 ባንኮች ከ68 ቅርንጫ ፎች እና ጀርመን 13 ባንኮች ከ70 ቅርንጫፎች ጋር«ብቻ» ነበሯቸው[68] ።የአሜሪካ ካፒታሊስቶች በተራቸው በእንግ ሊዞችና በጀርመኖች « በደቡብ አሜሪካ » በ1915 ዓ. ም. እሮሮ ባሠሙበት ወቅት « አምስት የጀርመን ባንኮች አርባ ቅርንጫፎች አሏቸው ፣ አምስት የእንግሊዝ ባንኮች ሰባ ቅርንጫፎች አሏቸው . . . . . እንግሊዝና ጀር መን ፣ ባለፉት ሃያ አምስት አመታት ውስጥ በግምት አራት ሺህ ሚሊዮን ዶላር ፣ በአርጀንቲና በብራዚልና በኡራጓይ ሥራ ላይ በማዋል የሶስቱን ሀገሮች ጠቅላላ ንግድ 46 እጅ ከመቶውን ይዘዋል[69] ።»

በማለት ይመቀኟቸዋል ። ወረትን ወደውጭ የሚ ልኩ ሀገሮች ዓለምን በመካከላቸውበመመጻደቅ አነጋገር ተከፋፍለዋታል ። ይሁን እንጂ ገንዘባዊ ወረት ወደዓለም በውን መከፋፈል አምርቷል ።

## ምዕራፍ አምስት

# የዓለም በካፒታሊስት ሕብረቶች መካከል መከፋፈል ፤

ሞኖፖላዊ ካፒታላዊ ማኅበራት ፣ ካርቴሎች ሲን ዲኬቶችና ትረስቶች ፣ በመጀመሪያ የሀገራቸውን ውስጥ ገበያ ተከፋፈሉ ፣ በተጨማሪም በሀገራቸው ውስጥ ያለ ውን ኢንዱስትሪ ከሞላ ጐደል በቁጥጥራቸው ስር አዋሉ። ይሁን እንጂ በካፒታሊዝም ውስጥ የሀገር ውስጥ ገበያ ከውጪ ሀገር ገበያ ጋር የተያያዘ ነው ። ካፒታሊዝም ከብዙ

ጊዜ በፊት የዓለምን ገበያ ፈጥሯል ። የወረት ወደ ውጭ መላክ በጨመረ መጠን ፣ በተጨማሪም ከውጪ ሀገር ችና ከቅኝ ግዛቶች ጋር ያለው ግንኙነት ብሎም የታላላቅ ሞኖፖሊስት ማህበራት « የተጽዕኖ አካባቢዎች » (ስፌርስ ኦፍ ኢንፍሉዌንስ) በያቅጣጫው እስከተስፋፉ ድረስ ሁሉም ነገር በነዚህ ማኅበራት ወደሚደረግ ዓለም አቀፍ ስምምነትና ዓለም አቀፍ ካርቴሎች ወደመመሥረት ያዘነብላል ።

ይህ በፊት ከነበረው ደረጃ ጋር ሲወዳደር በጣም ከፍ ያለ ፣ አዲስ የወረትና የምርት ዓለም አቀፍ ድልበት ደረጃ ነው ። እስቲ ይህ ከፍተኛ ሞኖፖሊ (ሱፐር ሞኖፖሊ) እንዴት እንደሚያደድግ እንመልከት ።

የኤሌክትሪክ ኢንዱስትሪ ፣ የዘመናዊው የቴክኒክ ውጤት ፣ የአሥራ ዘጠነኛው ምዕተ ዓመት መጨረሻና የሃያኛው ምዕተ ዓመት መግቢያ ካፒታሊዝም በጣም አይነተኛ ምልክት ነው ። ይህ ኢንዱስትሪ በጣም የተስፋፋው በሁለቱ የአዲሶቹ የካፒታሊስት ሀገሮች መሪዎች በሆኑት በአሜሪካና በጀርመን ነው ። በጀርመን ፣ እስከ 1900 ዓ.ም. ድረስ የነበረው ቀውስ ለዚህ ኢንዱስትሪ መድለብ ከባድ ግፊት ሠጥቶታል ። በዚህ ቀውስ ወቅት በዚያን ሰዓት በሚገባ ተጠናክረው ከኢንዱስትሪው ጋር ተዋሀደው የነበሩትን ባንኮች ፣ በአንጻራዊ አመለካከት አነስተኛ የነበሩትን ኢንዱስትሪዎች ጨርሶ መውደምና በትልልቆቹ መዋጥ በከፍተኛ ደረጃ አፋጥነው አክርረውትም ነበር ። « ባንኮች » ይላል ጄይድልስ ሲጽፍ «የወረት ከፍተኛ ፍላጐት ላላቸው ኢንዱስትሪዎች የእርዳታ እጃቸውን ለመዘርጋት ከመቆጠባቸውም በላይ ፣ ከነሱ ጋር የቀረበ ግንኙነት በሚገባ ባልመሠረቱት ኩባንያዎች ላይ ፣ በመጀመሪያ ቅጥ ያጣ ንረት ከዚያም ተስፋ አስቆራጭ ውድቀት አደረሱባቸው*።[70] »

በዚህም ሳቢያ ከ1900 ዓ. ም. በኋላ ፥ በጀርመን ድልበት በከፍተኛ እርምጃ ተስፋፋ ። እስከ 1900 ዓ. ም. ድረስ ሰባት ወይንም ስምንት የኤሌክትሪክ ኢንዱስትሪ «ምድቦች» ነበሩ ። እያንዳንዱ ምድብ በውስጡ በርካታ ኩባንያዎች (በጠቅላላው 28) ነበሩት ፥ እያንዳንዱም ቁጥራቸው ከ2 እስከ11 በሚደርስ ባንኮች ይደገፍ ነበር ። በ1908 ዓ.ም. እና በ1912 ዓ. ም. መካከል እነዚሁ ሁሉ ምድቦች በሁለት ወይንም በአንድ ምድብ ስር ተዋሃዱ ። ቀጥሎ የተመለከተው ስእላዊ መግለጫ ሂደቱን ያመለክታል ።

የኤሌክትሪክ ኢንዱስትሪ ምድቦች ፥—
ከ1900 በፊት ፤

ፌልተንና ጊውሎም | ላህሜየር | አንድነት ኤ.ኢ.ጂ | ሲመንስና ሀልስከ ኩ. | ሹከርት | በርግማን | ኩመር

ፌልተንና | ላህሜየር | ኤ.ኢ.ጂ (ጂ.ኢ.ሲ) | ሲመንስና ሀልስከ ሹከርት | በርግማን | በ1900ጠፋ

በ1912 ፥

ኤ.ኢ.ጂ (ጂ.ኢ.ሲ) ሲመንስና ሀልስከ—ሹከርት
(1908 ወዲህ «በጋራ» መሥራት ጀመሩ)

በዚህ አኳኋን ያደገው ዝነኛው ኤ. ኢ. ጂ(ጄኔራል ኤሌክትሪክ ኩባንያ) ፥ ከ175 እስከ 200 ኩባንያዎችንና (« በይዞታ » ሥርአት አማካይነት)እስከ 1,500 ሚሊዮን ማርክ የሚደርስ ወረት ይቆጣጠራል ። በውጪ ቀጥታ ወኪሎች በኩል ፥ ከአሥር በሚበልጡ ሀገሮች ውስጥ ፥ አሥራ ሁለቱ ውሑድ ድብል ኩባንያዎች የሆኑ ሠላሣ አራት ወኪሎች አሏቸው ። በ1904 ዓ. ም. በጀርመን የኤሌክትሪክ ኢንዱስትሪ በውጪ ከሥራ ላይ የዋለው ወረት ልክ ወደ 233 ሚሊዮን ማርክ እንደነበር ተገምቷል ።

ከዚህ ድምር ውስጥ 63 ሚሊዮን በሩሲያ ነበር በሥራ ላይ የዋለው ። ኤ ኢ. ጂ ፣ ከኬብሎችና ኢንሱሌተሮች (እሳተ ከላ) ጀምሮ እስከ ተሽከርካሪዎችና አውሮፕላኖች ድረስ የተለያዩ ዕቃዎችን የሚሠራ ታላቅ « ቅንጅት » የፋብሪካ ኩባንያዎች ብቻ ከአሥራ ስድስት አለማነሳቸውን መጥቀስ የሚያስፈልግ አይመስለንም ። ይሁን እንጂ በአውሮፓ የነበረው ድልቤት ፣ ቀጥሎ በተመለከተው መንገድ የተስፋፋው በአሜሪካ የነበረው የድልበት ሒደት አካል ነበር ።

ጀኔራል ኤሌክትሪክ ኩባንያ

| | | |
|---|---|---|
| አሜሪካ | ቶምሶን—ሂውስተን ኩባንያ በአውሮፓ አንድ ተቋም ይቋቋማል | ኤዲሰን ኩባንያ በአውሮፓ የፈረን ሳይ ኤዲሰን ኩባንያ የተባለውን ፈቃድ ለጀርመን ተቋም ሊያስተላልፍ የሚችለውን ይመሠርታል |
| ጀርመን | ዩኒየን ኤሌክትሪክ ኩባንያ | ጀኔራል ኤሌክትሪክ ኩባንያ /ኤ.ኢ:ጂ/ |

ጀኔራል ኤሌክትሪክ ኩባንያ (ኤ.ኢ.ጂ)

በዚህ ዓይነት ሁለት ኤሌክትሪካዊ « ታላላቅ ኃይሎች » ተመሠረቱ ። « በዓለም ውስጥ ፣ የሁለቱ ጥገኛ ሣይሆን የተመሠረተ አንድም የኤሌክትሪክ ኩባንያ የለም» ይላል ሄይኒግ « የኤሌክትሪክ ትረስት ፈለግ » በሚለው መጽሐፉ ውስጥ ። ተሟላተው ያልቀረቡ ቢሆንም የሚከተሉት አሐዞች ፣ ስለሁለቱ ትረስቶች የተቋም መጠንና የሽያጭ ግብር ፣ ትንሽ ሀሣብ ይሠጣሉ ።

| | | የሽያጭ ግብር /000,000 ማርክ/ | የሠራተኛ ብዛት | የተጣራ ትርፍ /000,000 ማርክ/ |
|---|---|---|---|---|
| አሜሪካ፤ጄኔራል ኤሌክትሪክ | | | | |
| ኩባንያ /ጄ.ኢ.ሲ/…… | 1907 | 252 | 28,000 | 35.4 |
| | 1910 | 298 | 32,800 | 45.6 |
| ጀርመን ጄኔራል ኤሌክትሪክ | | | | |
| ኮ/ኤ.ኢ.ጂ./ | 1907 | 216 | 30,700 | 14.5 |
| | 1911 | 362 | 60,800 | 21.7 |
| | 7 | 5 | 3 | 5 |

ከዚህ በኋላ ፣ በ1907 ዓ. ም. የጀርመንና የአሜሪካን ትረስቶች ዓለምን በመካከላቸው የተከፋፈሉበትን አንድ ስምምነት ተፈራረሙ ። በመካከላቸው የነበረው ውድድር አከተመ ። የአሜሪካው ጄኔራል ኤሌክትሪክ ኩባንያ(ጂ. ኢ. ሲ) የተባበሩት አሜሪካንና ካናዳን « አገኘ » ። የጀርመኑ ጄኔራል ኤሌክትሪክ ኩባንያ(ኤ. ኢ. ጂ) ጀርመንን፣ አውስትሪያን ፣ ሩሲያን ፣ ሆላንድን ፣ ዴንማርክና ስዊዘርላንድን ፣ ቱርክንና የባልካን ሀገሮችን « አገኘ » ። «ግልገል ኩባንያዎችን» ከዚህ በፊት ባልተመደቡ « አዳዲስ » ሀገሮች ውስጥ ወደቅርንጫፍ ኢንዱስትሪ የመቀየሩን እቅድ በሚመለከት በሚስጥር የተጠበቁ ልዩ ልዩ ስምምነቶች ተፈረሙ ። ሁለቱ ትረስቶች አዳዲስ የፈጠራ ክንውኖችንና ሳይንሳዊ ሙከራዎችን ሊለዋወጡ ነበር[71] ።

ከዚህ ግለኛና በዓለም ዙሪያ ከተንሠራፉ « በቅርንጫፎች » ፤ በወኪሎች ፣ በኤጀንቶች ፣ በግንኙነቶች ፣ ወዘተ አማካይነት የብዙ ሺህ ሚሊዮን ወረት በቁጥጥሩ ሥር ከዋለ ትረስት ጋር መወዳደር ምን ያህል አስቸጋሪ እንደሆነ ግልጽ ነው ። ይሁንና የዓለም በሁለት ኃያላን ትረስቶች መከፋፈል ፣ በጦርነት ፣ በኪሣራ ፤ ወዘተ ምክንያት ዕድገቱ ባለመስተካከሉ የሃይላት ግንኙነት ከተለዋ

ወጠ ፣ መልሶ መከፋፈልን አያስቀርም ። ለዚህ ዓይነቱ የእንደገና መከፋፈል ሙከራና ትግል ትምህርታዊ ምሣሌ ነትን ሊሠጥ የሚችለው የዘይት ኢንዱስትሪ ነው ። «የዓለም የዘይት ገበያ» ይላል በ1905 ዓ.ም. ጂይድልስ ሲጽፍ «አሁንም ቢሆን በሁለት ኃያላን ገንዘባዊ ቡድኖች ማለትም በሮክፌለሩ የአሜሪካ ስታንዳርድ ኦይል ኩባንያ እና ሮት ስቻይልድና ኖቤል ፣ ባኩ የሚገኘው የሩሲያ የዘይት ጉድጓዶች የመቆጣጠሪያ ድርጅት መሀል ፣ እንደተከፋፈለ ነው። ሁለቱ ቡድኖች የቀረበ ግንኙነት አላቸው ። ያም ሆኖ አምስት ተቀናቃኞች ለብዙ አመታት ሞኖፖሊያቸውን ስጋት ላይ ጥለውት ነበር[72] ። »

1. የአሜሪካን የዘይት ጉድጓዶችን መሟጠጥ ፣
2. የባኩ የማንታሼቭ ተቋም ውድድር ፣
3. የአውስትሪያ የዘይት ጉድጓዶች ፣
4. የሩማንያ የዘይት ጉድጓዶች ፣
5. የባህር ማዶ የዘይት ጉድጓዶች ፣ በተለይም በጀርመን ቅኝ ግዛቶች (ከመጠን በላይ ባለጸጋዎቹ ተቋሞች ከእንግሊዝ ወረት ጋር የተያያዙት ሳሙኤልና ሼል)። የመጨረሻዎቹ ሶስቱ ቡድኖች በታላቁ ዶቼ ባንክ ከሚመሩ የጀርመን ባንኮች ጋር ግንኙነት አላቸው ። እነዚህ ባንኮች በሩማኒያ ለምሳሌ ፣ እግራቸውን ለማስገባት ሲሉ ፣ « በግላቸውና » እቅድ ባለው መንገድ አንድ የዘይት ኢንዱስትሪ አቋቁመዋል ። በ1907

ዓ. ም. በሩማንያው የዘይት ኢንዱስትሪ ሥራ ላይ እንዲውል ከተደረገው በግምት የ185 ሚሊዮን ፍራንክ የውጪ ወረት ውስጥ 74 ሚሊዮን ፍራንክ ከጀርመን ወረት የመጣ ነበር[73] ።

በምጣኔ—ሀብት ሥነ ጽሑፍ እንደተጠቀሰው ሁሉ «ዓለምን ለመቀረማመት» ትግል ተጀመረ ። በአንድ ወገን የሮክፌለር « የዘይት ትረስት » በሁሉም ነገር ላይ እጁን ለማሣረፍ ፈለገ ። በሆላንድ በራስዋ ውስጥ « ግል ገል ኩባንያ » በመመሥረት ፣ ቀንደኛ ጠላቱን የእንግሊዝና የዳች የሼል ትረስትን ቀንዱን ለመምታት በደች ኢንዲስ የዘይት ጉድጓዶችን ገዛ ። በሌላ ወገን የደች ባንክና ሌሎች የጀርመን ባንኮች ሩማንያን «በይዞታቸው ሥር» ለማቆየትና ሮክፌለርን ለመቋቋም ከሩሲያ ጋር ለማበር ዕቅድ አወጡ ። ሮክፌለር የበለጠ ወረትና በጣም የተቀነባበረ የማጓጓዣና የማከፋፈያ ተቋም ነበረው ። በደች ባንክ ፈጽሞ መረታት፥ሁለት አማራጭ ስለነበረው ፣ ይኸውም ወይ « የዘይት ተቋሙን » መዝጋትና በሚሊዮን የሚቆጠር ወረት ማጣት ፣ ወይንም እጁን መስጠት ፣ ትግሉ ፈጽሞ ማቆምና በኋላም በ1907 ዓ. ም. መሞት ነበረበት ። እጅ መሥጠቱን በመምረጥ ከ« ዘይቱ ትረስት » ጋር አንድ ጉዳት ላይ የሚጥለው ስምምነት አደረገ ። « የአሜሪካንን ፍላጐት ሊጐዳ የሚችል ምንም ነገር ላለማድረግ » የደች ባንክ ተስማማ ። ጀርመን ምናልባት አንድ የመንግሥት የዘይት ሞኖፖሊ ብታቋቁም ስምምነቱን ለመሠረዝ የሚያስችል ሁኔታ ተደረገ ።

ከዚያ በኋላ « የዘይት ኰሜዲ» ተጀመረ ። ከንዘብ ንጉሶች አንዱ ቮን ግዊነር ፣ የዳች ባንክ ዳይሬክተር ፣ በጸሐፊው በስታውስ አማካይነት፥የመንግሥት የዘይት ሞኖፖሊ ለማቋቋም ዘመቻ ጀመረ ። የታላቁ የጀርመን ባንክ ግዙፉ መኪናና«ዘርፎች » ሁሉ መንቀሣቀስ ጀመሩ ። ጋዜጦች ፣ የአሜሪካንን « ቀንበር » በመቃወም « አርበኝነት » በተሞላበት ቁጭት መደንፋት ጀመሩ ። እና በመጋቢት 15 ቀን 1911ዓ.ም. ፓርላማው በጣም ከፍተኛ በሆነ ድምጽ

የተደገፈ የዘይት ሞኖፖሊን ትረስት ለማቋቋም የሚያስ ችል ሕግ እንዲያወጣ ለመንግሥት ጥያቄ አቀረበ ። መን ግሥቱ ይህንን « የሕዝብ » ሀሣብ እና አሜሪካዊውን ተቀናቃኙን ለማታለልና በመንግሥት ሞኖፖሊ ሥራ ውን ለማሻሻል ተስፋ አድርጎ በነበረው በዶች ባንክ ጨዋታ የውጥር በመያዙ የተሸነፈ መሠለ ። የጀርመን የዘይት ድርጅቶች ፣ ከሩሲያ የስኳር ማጣሪያ ትርፍ ሊያ ንስ የማይችል ከፍተኛ ትርፍ ከፊታቸው ተደቅኖ ታያ ቸው ። ይሁን እንጂ ሲጀመር ትልልቅ የጀርመን ባንኮች በዝርፊያው ክፍያ ላይ እርስ በርሳቸው መናጨት ጀመሩ። ዲስኮንቶ ጄስልሻፍት የዶችን ባንክ ስግብግብ ዓላማ አጋ ለጠ ፣ በሁለተኛ ደረጃ መንግስቱ ከሮክፌለር ጋር ሊያጋ ጥም የሚችለው ትግል ስጋት አሳደረበት ፣ ምክንያቱም ጀርመን ነዳጅ ከሌላ ቦታ ለማግኘት እርግጠኛ መሆኗ አጠራጣሪ ነበር ፣ (ከሩማንያ የሚገኘው የዘይት ምርት ጥቂት ነበር ) ። ሶስተኛ ፣ ልክ በዚያው ወቅት ፣ ለጀርመን የጦርነት ዝግጅት ፣ የ1913ቱ በሚሊዮን የሚቆጠር ማርክ ዱቤ ላይ ምርጫ ተደረገበት ። የዘይቱ ሞኖፖሊ እቅድ ለሌላ ጊዜ ተላለፈ ። ለጊዜውም ቢሆን የሮክፌለር « የዘ ይት ትረስት » ከትግሉ በድል አድራጊነት ወጣ ።

የበርሊን መጽሔት ፣ ዳይ ባንክ ፣ ጀርመን የዘይቱን ትረስት ለመዋጋት የምትችለው የኤሌክትሪሲቲ ሞኖ ፖሊ በማቋቋምና የውሃን ሃይል ወደርካሽ ኤሌክትሪ ሲቲ በመቀየር ብቻ መሆኑን ገልጾ ጽፏል ። « ግን » ይላል ደራሲው በመቀጠል « የኤሌክትሪሲቲ ሞኖፖሊ አምራቾቹ ሲፈልጉት ይቋቋማል ፣ ይህም ማለት ፣ የሚቀ ጥለው የኤሌክትሪክ ኢንዱስትሪ ውድቀት የማይቀር ሆኖ ሲታይና ከአንዳንድ ከተሞች መንግሥታት ፤ ወዘተ የዘ ግንት ሙብት በማግኘት ላይ ያሉ የግል የኤሌክትሪክ ድር

ጅቶች በያለበት በከፍተኛ ወጪ እያቋቋሚቸው ያሉት ግዙፍ የኃይል ማመንጫ ጣቢያዎች ትርፍ ማስገኘት ሲያ ቆሙ ነው ማለት ነው ። ከዚያ በኋላ የውሃ ኃይል አገልግ ሎት ላይ መዋል ይጀምራል ። ይሁን እንጂ ፣ በመንግሥት ኪሣራ ውሃን ወደርካሽ ኤሌክትሪሲቲ ለመቀየር አይ ቻልም ። በተጨማሪ ሥራው ፣ በመንግሥት ቁጥጥር ሥር ሳለ አንድ የግል ሞኖፖሊ መሠጠት አለበት ፣ ምክንያ ቱም ፣ የግል ኢንዱስትሪዎች በርካታ ውሎች የተፈራ ረሙ ስለሆነና ከፍተኛ ክፍያ እንደሚያገኙ ስለሚያውቁ ነው ። በናይትሬት ሞኖፖሊም እንደዚሁ ነበረ ፣ በዘይት ሞኖፖሊም እንደዚሁ ነበር ፣ በኤሌክትሪክ ኃይልም ሞኖ ፖሊ እንደዚሁ ይሆናል ። በማራኪ መርሐ ግብር አይና ቸው እንዲጋረድ የፈቀዱት የኛ መንግሥታዊ ሶሺያሊስ ቶች በጀርመን ሀገር ፣ ሞኖፖሊዎች ፣ ተጠቃሚውን ሕዝብ የመጥቀም ዓላማም እንዳልነበራቸውና በዚህም ምንም ውጤት እንዳላሳዩ ተረዱ ። ሌላው ቀርቶ ከመን ግሥት ለተደረገላቸው ድጋፍ የሚገባውን ትርፍ የመሥ ጠት ፍላጐት የላቸውም ። እነሱ ያደረጉት ነገር ቢኖር ኪሣራ ሊደርስባቸው የተቃረቡትን የግል ኢንዱስትሪ ዎች ፣ በመንግሥት ወጪ ፣ መልሰው እንዲያንሠራሩ ማድረግ ነው[74]» ።

እነዚህ ናቸው የጀርመን ቡርዧ ኤኮኖሚስቶች ተገ ደው የሚቀበሏቸው ጠቃሚ ሀቆች ። እዚህ ቁልጭ ብሎ የምናየው በገንዘባዊ ወራት የታሪክ ዘመን የግልና የመን ግሥት ሞኖፖሊዎች ፣ እንዴት አድርገው እንደሚቆላ ለፉ ነው ። ዓለምን ለመከፋፈል በታላላቅ ሞኖፖሊስቶች መካከል ለሚደረግ የኢምፔሪያሊስት ትንቅንቅ ሁለቱም እንዴት የተለያዩ ማያያዣዎች እንደሆኑ ነው ።

በንግድ መርከብም ፣ ከፍተኛው የድልበት ዕድገት ፣ የተፈጸመው ዓለምን በመከፋፈል ነበር ። በጀርመን ሁለት ኃያላን ኩባንያዎች ግንባር ቀደምትነቱን ይዘዋል ። እነ ዚህም እያንዳንዳቸው የ200 ሚሊዮን ማርክ (በስቶኮችና በጥቅሎች ወረት ያላቸውና ከ185 እስከ 189 ሚሊዮን ማርክ ኪራይ ሊያመጣ የሚችል የመርከቦች የመጫን ችሎታ ያኳቸው ሐምበርግ-አሜሪካ እና ኖርዱቸር ሎይድ ናቸው ። በሌላ በኩል በአሜሪካ በጥር 1 ቀን 1903 ዓ. ም. የሞርጋን ትረስት በመባል አለም አቀፍ የባህር ንግድ ኩባ ንያ ተቋቋመ ። ዘጠኙ የአሜሪካንና የእንግሊዝን የእንፋ ሎት መርከብ ኩባንያዎችን ከማዋሃዱም በላይ የ120 ሚሊዮን ዶላር (480 ሚሊዮን ማርክ) ወረት ነበረው ። ቀያም ብሎ በ1903 ዓ. ም. የጀርመን ጭራቆችና ይኸ የአሜሪካንና የእንግሊዝ ትረስት አለምን በመከፈል ትርፍን ለመከፋፈል ስምምነት አደረጉ ። የጀርመን ኩባ ንያዎች ከእንግሊዝና ከአሜሪካ ንግድ ጋር ላለመወዳደር ወሰኑ ። ለእያንዳንዱ የትኛው ወደብ እንደሚመደብለት ታወቀ ፣ ተቆጣጣሪ የጋራ ኮሚቴ ተቋቋመ ፤ ወዘተ . . . ስምምነቱም በጦርነት ጊዜ ሊሠረዝ የሚያስችልአንቀጽ በጥንቃቄ ታክሎበት ለሃያ ዓመት እንዲያገለግል ተደርጎ ተፈረመ[75] ።

ሌላው ከፍተኛ ትምህርት ሊሠጥ የሚችለው ደግሞ የአለም አቀፍ የባቡር ካርቴል አመሠራረት ታሪክ ነው ። የመጀመሪያው የእንግሊዝ ፣ የቤልጂየምና የጀርመን የባ ቡር ሐዲድ አፈብራኪዎች ፣ ካርቴል ለመመሥረት ያደ ረጉት መኩራ በ1884 ፣ ከፍተኛ የኢንዱስትሪ ውድቀት በደረሰበት ጊዜ ነበር ። አፈብራኪዎቹ በየሚመለከታቸው ሀገሮች ውስጥ ላሉት የሀገር ውስጥ ገበያዎች እርስ በርሳ ቸው ላለመወዳደር ስምምነት አደረጉ ፣ እና የውጪውን

ገበያ በሚከተለው ኮታ መሠረት ተከፋፈሉ ። ታላቋ ብሪታንያ 66 እጅ ከመቶ ፣ ጀርመን 24 እጅ ከመቶ ፣ ቤልጅየም 7 እጅ ከመቶ ፣ ህንድ ሙሉ በሙሉ ለታላቋ ብሪታንያ እንድትሰጥ ተደረገ ። በማናቸውም ካርቴል ውስጥ ባልገባ የእንግሊዝ ተቋም ላይ የጋራ ጦርነት ለማካሔድ ፣ የጦርነቱንም ወጪ እንደሽያጫቸው በፐርሰንት አሥራት በማውጣት ለመክፈል አወጁ ። ይሁንና ካርቴሉ በ1886.ዓ.ም. ሁለት የእንግሊዝ ተቋሞች ከውስጡ ሲወጡ ፈረሰ ። በተከታዮቹ የንብረት ወቅቶች ስምምነት ሊደረግ እንደማይቻል የታወቀ ነው ።

በ1904 መግቢያ ላይ የጀርመን አረብ ብረት ሲንዲኬት ተመሠረተ ። በኅዳር 1904 አለም አቀፍ የባቡር ካርቴል በሚከተለው ኮታ መሠረት እንደገና እንዲንቀሣቀስ ተደርጎ እንግሊዝ 53.5 እጅ በመቶ፣ጀርመን 28.83 እጅ በመቶ ፣ ቤልጅየም 17.67 እጅ በመቶ ፤ ፈረንሣይ ዘግይታ ገብታ ለሚቀጥሉት ሶስት ዓመታት 4. 8 ፣ 5. 8 ፣ እና 6.4 በመቶ እጅ ጠቅላላውን ከ100 ፐርሰንት በላይ የሚደርስ ማለትም 104.8 እጅ በመቶ ፤ ወዘተ ... ድርሻ አገኙ ። በ1905 የተባበሩት አሜሪካ የአረብ ብረት ኮርፖሬሽን ካርቴሉ ውስጥ ገባ ። ከዚያም አውስትሪያና ስፓኝ ተከተሉ ። « በአሁኑ ጊዜ » ይላል ቮግልስቲን በ1910 «የዓለም መከፋፈል አብቅቷል ። «ከፍተኛ ተጠቃሚዎቹም፣ በመጀመሪያ የባቡር መሥመሮች ምክንያቱም ዓለም የተቀረማመተችው የነሱ ጥቅም ግምት ሣይሠጠው ነውና በጁፒተር ሰማዮች ላይ እንደሚኖር ባለቅኔ (ፓየት) መቀመጥ ይችላሉ**76 ። »

በ1909 የተመሠረተውንና የተገኘውን ትርፍ ለአምስት የፋብሪካ ምድቦች ፣ ለጀርመን ፣ ለቤልጅየም ፣ ለፈረንሣይ ፣ ለስፓኝ እና ለእንግሊዝ ፣ በትክክል ያደላደ

ለውን አለም አቀፍ የዚንክ ሲንዲኬትን ልጥቀስ ። ቀጥሎ ሊኤፍማን «በጣም ዘመናዊ ፣ በተመሣሣይ መንገድ ከተደራጁት የአሜሪካና የፈረንሣይ የፈንጂ አፈብራኪዎች ጋር መላውን ዓለም የተከፋፈለው ፣ በጀርመን ፈንጂ አፈብራኪዎች የቅርብ መረዳዳት የተመሠረተውን **77 » አለም አቀፍ የዲናሞ ትረስትን ይጠቅሳል ።

በ1897 የጀርመን ድርሻ ያለባቸው በጠቅላላው አርባ የሚሆኑ ዓለም አቀፍ ካርቴሎች እንደነበሩና በ1910 ቁጥራቸው ወደ አንድ መቶ እንደተጠጋ ሊኤፍማን አስልቶ ነበር ። አንዳንድ የቡርዧ ጸሐፊዎች ፣ (ቀደም ብሎ የነበረውን ፣ ለምሣሌ በ1909 ፣ የማርክሲስት አቋም ፈጽሞ የተወወውን ካርል ኮትስኪን ጨምሮ) ወረትን አለም አቀፋዊ የማድረግ ከፍተኛ ግምት የተሠጠው አገላለጽ ዓለም አቀፍ ካርቴሎች ፣ በካፒታሊዝም ወቅት በመንግሥታት መካከል ሰላምን ለማስገኘት ተስፋ አለው የሚል ሀሣብ ገልጠዋል ። ከንድፈ ሀሣብ አንጻር ሲታይ ይህ አባባል ፈጽሞ ትርጉም የለሽ ሲሆን ፣ በተግባር ደግሞ መሠረተቢስ የማታለያ ክርክርና ዋሾ ፣ የባሰ መጥፎ ለሆነው አድርባይነት መከላከያ ነው ። ዓለም አቀፍ ካርቴሎች ፣ የካፒታሊስት ሞኖፖሊዎች ዕድገት ከምን ደረጃ እንደደረሰና በአያሌ ካፒታሊስት ማህበራት መካከል የሚደረገው ትግል ለምን ዓላማ እንደሆነ ያሳያሉ ። ይህ የመጨረሻው ሁኔቴ በጣም ጠቃሚ ነው ። በመካሔድ ላይ ያለውን የታሪካዊ

ምጣኔ — ሀብትን ሁኔታ ትርጉም የሚየሣየው እሱ ብቻ ነው ። ምክንያቱም የትግሉ ቅርጾች በተለያዩ ልዩና ጊዜያዊ ምክንያቶች አንጻር በተከታታይ ሊለወጡ ይችሉ ይሆናል ፤ ግን የትግሉ ዋና ክፍል ፣ የመደብ ይዘቱ መደቦችእስካሉ ድረስ በርግጥ ሊለወጥ አይችልም ። ኮትስኪ በንድፈ ሀሣባዊ አቀራረቡ የተጎዳኛቸው የጀርመን ቡርዧዎች

(ስለኰትስኪ ሌላ ጊዜ እመለስበታለሁ) የአሁኑን ጊዜ ትግል መሠረተ ነገር (የዓለም መከፋፈል) ማድበስበስንና አንድ ጊዜ አንዱን ሌላ ጊዜ ደግሞ ሌላውን የትግል ቅርጽ ማጋነን ሥራችን ብለው መያዛቸው ሀቅ ነው ። ኰትስኪም ይህንኑ ሥህተት ይሠራል ። ይህን በምንልበት ጊዜ የምንነጋገረው ስለጀርመን ብቻ ሣይሆን ስለጠቅላላው የዓለም ቡርዧ ነው ። ካፒታሊስቶች ዓለምን የሚከፋፍሉት ለአንድ የተለየ የጥፋት ዓላማ ሣይሆን ፣ የተደረሰበት የድልበት ብዛት ደረጃ ትርፍ ለማግኘት ይህን ዘዴ እንዲጠቀሙበት አስገድዷቸው ነው ። በሸቀጥ ምርትና በካፒታሊዝም ውስጥ የመከፋፈያ ዘዴ ስለሌለ ፣ ክፍፍሉን « በወረታቸው መጠንና » « ባላቸው የኃይል መጠን » ነው የሚያከናውኑት ። ይሁንና ፣ ኃይል ከምጣኔ-ሀብታዊና ከፖለቲካዊ የዕድገት ደረጃ ጋር ይለያያል ። የሚሆነውን ነገር ለመረዳት በኃይል መሻሻል አማካይነት ምን ምን ጥያቄዎች መልስ እንዳገኙ ማወቅ ያሻል ። እነዚህ መሻሻሎች « ንጹህ » ምጣኔ-ሀብታዊ ወይንም ምጣነ ሀብታዊ ያልሆኑ (ወታደራዊ) የመሆናቸው ጥያቄ በሁለተኛ ደረጃ የሚታይ በመጨረሻው የካፒታሊዝም የታሪክ ዘመን መሠረታዊ አመለካከት ላይ ለውጥ ሊያመጡ የማይችሉ ከመሆናቸው ላይ ነው ። የትግሉንና የስምምነቱን (ዛሬ ሠላማዊ ፣ ነገ ውጊያ ፤ በሚቀጥለው ቀን ውጊያ እንደገና) ቅርጽ ጥያቄ በካፒታሊስት ማህበራት መካከል ባለው የትግልና የስምምነት ይዘት ጥያቄ መቀየር ወደአጭበርባሪነት ሚና መሥመጥ ነው ።

የመጨረሻው የካፒታሊስት የታሪክ ወቅት ደረጃ ፣ በካፒታሊስት ማኅበራት መካከል ያለው ግንኙነት ፣ በምጣኔ-ሀብታዊ የዓለም መከፋፈል ላይ ተመሥርቶ ፣ እንደሚያድግ ያሣየናል ። ከእሱ ጋር ጐን ለጐን ወይንም ተያ

ይዘው ፣ በፖለቲካዊ ተራድኦ ፣ በመንግሥታት መካከል ፣ ዓለምን በግዛት መከፋፈል ላይ ፣ ለቅኝ ግዛት በመታገል ላይ ፣ « ለተጽዕኖ አካባቢዎች በመታገል » ላይ ተመሥርተው የሚያድጉ አንዳንድ ግንኙነቶችም አሉ ።

## ምዕራፍ ስድስት

# የዓለም በኃያላን መንግሥታት መካከል መከፋፈል

ስለ « የአውሮፓውያን ቅኝ ግዛቶች የግዛት ዕድገት » በጻፈው·መጽሐፉ ውስጥ የመልክዓ ምድሩ ሊቅ[78] ኤ·ሱፓን ስለዚሁ ዕድገት በአሥራ ዘጠኝ መቶ ምዕተ ዓመት መጨረሻ ላይ የሚከተለውን አጭር ማጠቃለያ አቅርቧል ። በአውሮፓውያን የቅኝ ገዢዎች ይዞታ ሥር ያለውን ግዛት በመቶ የሚያሣይ ሠንጠረዥ(የተባበሩት አሜሪካን ጨምሮ)

| | 1876 (በመቶ) | 1900 (በመቶ) | በመጨመር ወይም በመቀነስ |
|---|---|---|---|
| አፍሪካ . . . . . . | 10.8 | 90.4 | + 79.6 |
| ደቡብ ምሥራቅ እስያ | 56.8 | 98.9 | + 42.1 |
| እስያ . . . . . . | 51.5 | 56.6 | +5.1 |
| አውስትራሊያ . . | 100.00 | 100.00 | — |
| አሜሪካ . . . . | 27.5 | 27.2 | —0.3 |

« የዚህ ወቅት መለያ ባህርዩ » ይላል ደራሲው ሲደመድም «የአፍሪካና የደቡብ ምሥራቅ እስያ መከፋፈል

ነው » በአሜሪካና በእስያ ውስጥ ያልተያዙ ግዛቶች ፣ ማለትም የአንድ መንግሥት ይዞታ ያልሆኑ ስለሌሉ ፣ ከሱፓን ማጠቃለያ ይህንን ወቅት የዓለም መከፋፈያ የመ ጨረሻ ወቅት ብሎ መናገር ይቻላል ። መጨረሻም ስንል እንደገና መልሶ መቀራመት የለም ማለታችን ሣይሆን ፣ መልሶ መቀራመት የሚቻልና የማይቀርም ስለሆነ ፣

የካፒታሊስት አገሮች በዓለማችን ውስጥ ያልተያዙ ግዛ ቶችን የመያዝ የቅኝ ግዛት ፖሊሲ አከተመ ማለታችን ነው ። ዓለም ለመጀመሪያ ጊዜ ፊጽማ ተከፋፈለች ። ስለ ሆነም ወደፊት መልሶ መከፋፈል ይቻላል ፣ ማለትም ግዛ ቶች ከአንዱ « የቅኝ ገዥ » ወደ ሌላው መተላለፍ ይች ላሉ እንጂ አዲስ የቅኝ ገዢ ሊኖራቸው አይችልም ስለ ዚህ ፣ « በካፒታሊዝም የመጨረሻ የዕድገት ደረጃ » ከገን ዘባዊ ወረት ጋር በቅርብ በተያያዘ ፣ በዓለም የቅኝ ግዛት ፖሊሲ ታላቅ ወቅት ፣ ውስጥ ነው የምንገኘው ። ይህም በመሆኑ ፣ የጊዜውን ሁኔታ ምንነትና ይህ የከፍተኛ ድር ጊት ዘመን ቀደም ብለው ከነበሩት ተመሣሣይ ወቅ ቶች የሚለይበትን በተቻለ መጠን ለማረጋገጥ ፣ እንዚህን እውነታዎች በሰፊው መረዳት በጣም አስፈላጊ ነው ። በመጀመሪያ ደረጃ ሁለት የእውነታ ጥያቄዎች ይነሣሉ ። እነሱም ፤

1. የቅኝ ግዛት ፖሊሲ መጠናከር ፣ ማለትም ለቅኝ ግዛቶች ሽሚያ የሚደረገው ትግል ከፍተኛ ደረጃ መድረስ በርግጥ የተከሰተው በገንዘ ባዊ ወረት ዘመን ነውን ?

2. ከሆነስ እንዴት ነው ዓለም በአሁኑ ጊዜ የተከ ፋፈለችው ? የሚሉ ናቸው ።

አሜሪካዊው ጸሐፊ ሞሪስ[79] ስለ ቅኝ ግዛት በጻፈው መጽሐፉ ውስጥ በአሥራ ዘጠነኛው ክፍለ ዘመን በተለያየ ወቅት ታላቋ ብሪታንያ ፣ ፈረንሣይና ጀርመን ይዘዋቸው ስለነበሩት ቅኝ ግዛቶች የተሰበሰበውን ሐቅ ለማጠቃለል ሙከራ አድርጓል ። ቀጥሎ የተመለከተው ይህ ሰው የሰበሰበው አጭር ማጠቃለያ ነው ።

## የቅኝ ግዛት ይዞታ

| ዘመን | ታላቋ ብሪታንያ | | ፈረንሣይ | | ጀርመን | |
|---|---|---|---|---|---|---|
| | የመሬት ስፋት በሚሊዮን ሜትር ካሬ | የሕዝብ ብዛት በሚሊዮን | የመሬት ስፋት በሚሊዮን ሜትር ካሬ | የሕዝብ ብዛት በሚሊዮን | የመሬት ስፋት በሚሊዮን ሜትር ካሬ | የሕዝብ ብዛት በሚሊዮን |
| 1815—30 | ? | 126.4 | 0.02 | 0.5 | — | — |
| 1860——— | 2.5 | 145.1 | 0.20 | 3.4 | — | — |
| 1880——— | 7.7 | 267.9 | 0.70 | 7.5 | — | — |
| 1899——— | 9.3 | 3.70 | 3.70 | 56.4 | 1.0 | 14.7 |

ለታላቋ ብሪታንያ ፣ ከፍተኛው የቅኝ ግዛት ማስፋፋት የተደረገበት ወቅት ከ1860 ዓ. ም. እስከ 1880 ዓ.ም. ያለው ጊዜ ሲሆን በአሥራ ዘጠነኛው ምዕተ ዓመት የመጨረሻ ሃያ ዓመታት የተደረገውም መስፋፋት በቀላሉ የሚገመት አይደለም ። ለፈረንሣይና ለጀርመን ደግሞ ይኸው መስፋፋት የተደረገው በነዚሁ የመጨረሻ ሃያ ዓመታት ውስጥ ነው ። የቅድመ ሞኖፖሊ ካፒታሊዝም ዕድገት ማለትም የነጻ ውድድር የሰፈነበት ካፒታሊዝም በ1860 ዎችና በ1870 ዎች የመጨረሻ ደረጃው ደርሶ እንደነበር ተመልክተናል ። የቅኝ ግዛት ከፍተኛ ቅጽበታዊ ወረራ የተጀመረውም ሆነ ዓለምን በቅኝ ግዛት መከፋፈል ከፍ

ተኛ ደረጃ ላይ የደረሰው በትክክል ከዚህ ጊዜ በኋላ መሆኑን መመልከት ይቻላል ። የካፒታሊዝም ወደ ሞኖፖሊ ካፒታሊዝም ወደ ገንዘባዊ ወረት ፣ መሸጋገር ዓለምን ለመቀራመት ከሚደረግ የትግል መጠናከር ጋር የተያያዘ መሆኑ የሚያጠያይቅ አይሆንም ። ሆብሰን ፣ ስለኢምፔሪያሊዝም በጻፈው መጽሐፉ ውስጥ ከ1884 እስከ 1900 ዓ. ም. ድረስ ያለውን ጊዜ የዋና ዋናዎቹ የአውሮፓ መንግሥታት የከረረ መስፋፋት የታየበት ዘመን መሆኑን ጠቅሷል ። እሱም ባደረገው ግምት ታላቋ ብሪታንያ በነዚህ ዓመታት ውስጥ 57,000,000 ሕዝብ የሚኖርበት 3,700,000 ካሬ ማይልስ ስፋት ያለው ግዛት ይዛለች ። ፈረንሣይም 36,500,000 ሕዝብ የሚኖርበት 3,600,000 ካሬ ማይልስ ስፋት ያለው ግዛት ይዛለች ። እንዲሁም ጀርመን 14,700,000 ሕዝብ የሚኖርበት 1,000,000 ካሬ ማይልስ ስፋት ያለው ግዛት በዚሁ ጊዜ ውስጥ ይዛለች ። በተጨማሪም ቤልጅግ 30,000,000 ሕዝብ የሚኖርበት 900,000 ካሬ ማይልስ ስፋት ፣ ፖርቱጋል 9,000,000 ሕዝብ የሚኖርበት 800,000 ካሬ ማይልስ ስፋት ያላቸው ግዛቶች ይዘዋል ። በአሥራ ዘጠነኛው ምዕተ ዓመት መጨረሻ ገደማ በተለይም በ1880ዎቹ ዓመታት ካፒታሊስት መንግሥታት ለቅኝ ግዛት ሽሚያ ያደርጉት የነበረው እሽቅድምድም ፣ በዲፕሎማሲና በውጭ ጉዳይ ፖሊሲ ታሪክ ውስጥ በሰፊው የታወቀ ነው ።

ተቀዳሚ የእንግሊዝ የቡርዧ የፖለቲካ ሰዎች የቅኝ ግዛት ፖሊሲን በመቃወም፣ነጻ የገበያ ውድድር አብቦበት በነበረው በ1840 ዓ. ምና. በ1860 ዓ. ምህረቶች ውስጥ ፣ የቅኝ ግዛቶችን ነጻ መውጣት ማለትም ከእንግሊዝ ፈጽሞ መለያየታቸው አስፈላጊና የማይቀርም መሆኑን አስገንዝበው ነበር ። ኤም ቢር «ዘመናዊው የእንግሊዝ[80] ኢምፔሪ

ያሊዝም» በሚለው በ1898 ዓመተ ምሕረት በታተመው ጽሑፉ ውስጥ ዲዝራኤሌ የሚባለውና ባጠቃላይ ለኢምፔሪያሊዝም ዝንባሌ የነበረው ቀንደኛ መሪ « ቅኝ ግዛቶች በአንገታችን ላይ እንደተንጠለጠለ የወፍጮ ድንጋይ ናቸው » በማለት በ1852 መግለጫ ሰጥቶ ነበር ። ይሁን እንጂ በአሥራ ዘጠነኛው ምዕተ ዓመት መጨረሻ ላይ ኢምፔሪያሊዝምን በይፋ ያስተጋቡትና የኢምፔሪያሊዝምን ፖሊሲ ሀፍረተቢስ በሆነ አኳኋን በሥራ ላይ ያዋሉት የጊዜው የእንግሊዝ ጀግኖች ሲሰል ሮድስና ዮሴፍ ቻምበርሊን ነበሩ ።

እነዚህ የእንግሊዝ የቡርዧ የፖለቲካ መሪዎች በዚያን ጊዜም ቢሆን በንጹህ ምጣኔ-ሀብታዊና በዘመናዊው የኢምፔሪያሊዝም የሕብረተሰብ የፖለቲካ መሠረት መካከል ያለውን መያያዝ በደስታ ነበር የተመለከቱት ። ኢምፔሪያሊዝም «ትክክለኛ ፥ ብልህና ምጣኔ ሀብታዊ ፖሊሲ» እንደሆነና በተለይም ጀርመን ፥ አሜሪካንና ቤልጅግ በዓለም ገበያ ከታላቋ ብሪታንያ ጋር የሚያደርጉትን ግንኙነት ቻምበርሊን ያስተጋባ ነበር ። ካፒታሊስቶች ካርቴልን ሲንዲኬትንና ትረስትን ባቋቋሙበት ወቅት ቁጠባ ከሞኖፖሊ ይገኛል ብለው ነበር ። የቡርዧ የፖለቲካ መሪዎች ቅርምት ላይ ያላዋሉትን የዓለም ክፍሎች ለመ'ገጋት በሚሯሯጡበት ወቅት ቁጠባ ከሞኖፖሊ ይገኛል በማለት አስተጋብተው ነበር ። ሲሲል ሮድስ ከቅርብ ወዳጁ ከጋዜኛው እስቴድ በተገኘው መረጃ መሠረት ስለኢምፔሪያሊዝም ያለውን አስተያየት በ1895 ሲሰጥ እንዲህ ብሏል ። « ትናንት ከሎንደን በስተምሥራቅ ሜፍ (የሠራተኛው መደብ ሠፈር ) በአንድ ስብሰባ ተካፍዬ ነበር ። ዳቦ! ዳቦ! የሚል ጩኸት የተመላበት ንግግር አዳምጬ ነበርና ወደ ቤቴ በመሄድ ላይ እያለሁ ሁኔታውን ሳሰላስል ከመቸውም

ጊዜ ይልቅ አሁን የኢምፔሪያሊዝምን ጠቃሚነት መረዳት ቻልኩ ። ... ይህ የእኔ የተወደደው ሃሣብ ለኅብረ ተሰቡ ችግር መፍትሔ ነው ፣ ማለትም 40,000,000 ነዋሪዎች የሚኖሩባትን እንግሊዝ ከእርስ በርስ ጦርነት ለማዳን እኛ የቅኝ ገዢው መንግሥት ባለሥልጣኖች የተትረፈረፈውን ሕዝብ የምናሰፍርበት አዲስ መሬት ማግኘት አለብን ፣ ከፋብሪካዎችና ከማዕድኖች ለሚገኙት ዕቃዎችም አዲስ ገበያ ማዘጋጀት አለብን ። አዘውትሬ እንዳልኩት የሰፊ ግዛት ጥያቄ የዳቦና የቅቤ ጥያቄ ነው ። የርስ በርስ ጦርነትን ለማስወገድ ከተፈለገ መፍትሔው ኢምፔሪያሊስቶች መሆን ነው[81] »ይህን ያለው በ1895 ዓም ሚሊዮኑ የገንዘባዊ ንጉሥ ለእንግሊዞችና ዳች ጦርነት መነሳት ዋናው ምክንያት የነበረው ሲስልሮድስ ነበር ። እርግጥ ለኢምፔሪያሊዝም የሚያደርገው መከላከል ሀፍረተቢስና ግርድፍ ነው ። ይሁን እንጂ በይዘቱ እነ ማስሎቭ ፣ ሱዴኩም ፣ ፖትሪሰቭ ፣ ዳቪድ ፣ የሩሲያ ማርክሲዝም መሥራችና ሌሎችም ከሚያራምዱት ንድፈ-ሀሳብ አይለይም ። ሲስል ሮድስ ደህና ሕብረተሰባዊ ትምክህተኛ * ነበር ። የዓለምን በግዛት መከፋፈልና በዚህም አንጻር ባለፉት የአሥር ዓመታት ጊዜያት የደረሰውን ለውጥ ትክክለኛ ገጽታ ለማሣየት ያህል ከፍ ብሎ ተጠቅሶ ከነበረው ስለ ዓለም ኃያላን ቅኝ ግዛታዊ ይዞታ ከሚገልጸው የሱፓን ጽሑፍ የተገኘውን መረጃ ለመጠቀም እፈልጋለሁ ። ሱፓን 1876 ዓ. ም. እና 1900 ዓ. ም. ምህረትን ወስዷል ። እኔ ደግሞ ከሱፓን ሳይሆን 1876 ዓመተ ምህረትን ይበልጥ በቅርቡ ከቀረበው የሁብነርን «መልክአ ምድራዊና ስታትስቲካዊ ሠንጠረዥ » በመጠቀም በትክክል የተመረጠው ዓመተ ምሕረት የቅድመ ሞኖፖሊስት የምዕራብ አውሮፓ ካፒታሊዝም የዕድገት ደረጃ በትክክል በዚህ ጊዜ ነውና ያከተመው 1914 ዓመተ ምሕረትን እውስዳለሁ ። ሱፓን

መግለጫዊ አሀዞችን የሚጠቀመው ለቅኝ ግዛቶች ብቻ ነው ። የዓለምን መከፋፈል ትክክለኛ ገጽታ አሟልቶ ለማቅረብ ቅኝ ስላልሆኑና ከፊል ቅኝ ስለሆኑ አገሮች አጠር አጠር ያለ መረጃ ማከል ጠቃሚ ሆኖ አግኝቸዋለሁ ። ኢራን (በቀድሞ ስሙ ፐርሺያ) ቻይናንና ቱርክን በከፊል ቅኝ ግዛት ክፍል ነው የምመድባቸው ። ከነዚህም አገሮች የመጀመሪያው ከሞላ ጎደል ቅኝ ግዛት እየሆነ ነው ። የተቀሩትም ሁለቱ ወደ ሙሉ ቅኝ ግዛትነት እያመሩ ናቸው ።

ስለዚህ የሚከተለውን ውጤት እናገኛለን ።

የኃያላን መንግሥታት የቅኝ ግዛት ይዞታ (በሚሊዮን ካ. ሜ. ካሬ እና በሚሊዮን የሕዝብ ብዛት)

| ቅኝ ገዥ አገሮች | ቅኝ ግዛቶች | | | | የቅኝ ገዥ አገሮች ስፋትና ሕዝብ | | ድምር | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | 1876 | | 1914 | | 1914 | | 1914 | |
| | ስፋት | ሕዝብ | ስፋት | ሕዝብ | ስፋት | ሕዝብ | ስፋት | ሕዝብ |
| ታላቋ ብሪታንያ | 22.5 | 251.9 | 33.5 | 393.5 | 0.3 | 46.5 | 33.8 | 440.0 |
| ሩስያ | 17.0 | 15.9 | 17.4 | 33.2 | 5.4 | 136.2 | 22.8 | 169.4 |
| ፈረንሣይ | 0.9 | 6.0 | 10.6 | 55.5 | 0.5 | 39.6 | 11.1 | 95.1 |
| ጀርመን | — | — | 2.9 | 12.3 | 0.5 | 64.9 | 3.4 | 77.2 |
| የተባበሩት አሜሪካ | — | — | 0.3 | 9.7 | 9.4 | 97.0 | 9.7 | 106.7 |
| ጃፓን | — | — | 0.3 | 19.2 | 0.4 | 53.0 | 0.7 | 72.2 |
| የ6 ኃያላን ድምር | 40.4 | 273.8 | 65.0 | 523.4 | 16.5 | 437. 2 | 81.5 | 960.6 |
| /የቤልጂየም ፤ ሆላንድ ወዘተ/የሌሎች ኃያላን ቅኝ ግዛቶች | | | | | | | 9.9 | 45.3 |
| ከፊል ቅኝ ግዛቶች /ፐርሺያ ፥ ቻይና ፤ ቱርክ/ | | | | | | | 14.5 | 361.2 |
| ሌሎች አገሮች | | | | | | | 28.0 | 289.9 |
| የዓለም ጠቅላላ ድምር | | | | | | | 133.9 | 1657.0 |

በሠንጠረዥ ከሠፈሩት ቁጥሮች በሃያኛው ምዕተ ዓመት መግቢያ ላይ ዓለምን የመቀራመቱ ሥራ ምን ያህል የተጠናቀቀ እንደነበር በግልጽ መመልከት እንች ላለን ። ከ1876 ዓመተ ምሕረት በኋላ የቅኝ ግዛቶች ይዞታ በከፍተኛ መጠን ማለትም ከሃምሣ በመቶ እጅ በላይ ጨም ሯል ። ይህም በመሬት ስፋት መጠን ሲታይ ለስድስቱ ኃያላን መንግሥታት ከ40,000,000 ወደ 65,000,000 ኪ. ሜ. ካ. ከፍ ብሏል ። የ25,000,000 ኪሎ ሜትር ካሬ ስፋት ጭማሪ ከቅኝ ገዢዎቹ አገሮች ስፋት (16,500,000 ኪሎ ሜትር ካሬ) ጋር ሲነጻጸር በሃምሣ እጅ በመቶ ከፍ ብሏል ። በ1876 ሶስት ኃያላን አገሮች ምንም ቅኝ ግዛት ያልነበራቸው ከመሆኑም በላይ ፈረንሣይም ምንም እን ዳልነበራት ይቆጠራል ። ይሁንና በ1914 ዓመተ ምሕረት እነዚህ አራት አገሮች ስፋቱ 14,100,000 ኪሎ ሜትር ካሬ የሆነ ቅኝ ግዛት መያዛቸው ይታያል ። ይህም 100, 000,000 ሕዝብ ያለውን የአውሮፓን ስፋት ሁለት እጥፍ ይሆናል ። የቅኝ ግዛት ይዞታው አለመስተካከልም በጉ ልህ ይታያል ። ለምሣሌም ያህል በስፋትና በሕዝብ ብዛት እምብዛም የማይለያዩትን ፈረንሣይን ፣ ጀርመንንና ጃፓ ንን ብናወዳድር ፣ የመጀመሪያው አገር የሁለቱን አገሮች ቅኝ ግዛቶች በአንድነት በሶስት እጅ የሚበልጥ ቅኝ ግዛት እንደያዘ መገንዘብ ይቻላል ። በገንዘባዊ ወረት አንጻርም በተጠቀሰው ጊዜ የፈረንሣይ ፣ የጃፓንና የጀርመን የገን ዘብ ወረት ተዳምሮ ከነበራቸው ብዙ ጊዜ የበለጠ ሣይ ኖረው እንዳልቀረ ይታመናል ። ከምጣኔ–ሀብታዊው ሁኔታ በተጨማሪ ለቅኝ ግዛት ይዞታው ስፋት የቅኝ ገዢዎቹ አገሮች መልክዓ — ምድራዊና ሌሎችም ሁኔታዎች የሚ ጫወቱት ሚና ይኖራቸዋል ። በታላላቅ ኢንዱስትሪ ዎች ፣ በልውውጥና በገንዘባዊ ወረት ግፊት ምንም ያህል ዓለምን ለማስተካከል ፣ የምጣኔ—ሀብቱንና የኑሮ ደረጃን

ለማስተካከል የተደረገው እርምጃ ከፍተኛ ቢሆንም አሁንም ልዩነቶች ይታያሉ ። ስለሆነም ከላይ ከተጠቀሱት ስድስት ኃያላን መንግሥታት ገና ብቅ ያሉት ካፒታሊስት አገሮች(አሜሪካ ፣ ጀርመን ፣ ጃፓን) ዕድገት ከፍተኛ ፍጥነት እንደነበረው እናያለን ። በሁለተኛ ደረጃ ደግሞ የቀድሞ የካፒታሊስት ዕድገት የነበራቸው ሀገሮች ( ፈረንሣይና ታላቋ ብሪታንያ ) ከአዲሶቹ ጋር ሲነፃፀሩ በጣም ዘገምተኛ መሻሻል እንዳሳዩ ልንረዳ እንችላለን ። ሶስተኛ ደግሞ በምጣኔ—ሀብት በጣም ኋላቀር አገር (ሩሲያ) ዘመናዊው ካፒታሊስት ኢምፔሪያሊዝም ከቅድመ ካፒታሊስት የምርት ግንኙነት ጋር ተወሳስቦ የሚገኝበት አለ ።

ታላላቅ ኃያላን መንግሥታት ከያዟቸው ቅኝ ግዛቶች ጋር የትናንሾቹንም የቅኝ ይዞታዎች አስቀምጠናል ። እነዚህም ግዛቶች ምናልባት « መልሶ መከፋፈል » ላይ ሊውሉ ይችሉ ይሆናልና እነዚህ ትንንሽ ቅኝ ገዢዎች ይበልጡን ጊዜ ግዛቶቻቸውን እንደያዙ ይቆያሉ ። ምክንያቱም ኃያላኑ ቅኝ ገዢዎች የዘረፉትን ተስማምተው እንዳይከፋፈሉ የሚያደርጉ የሚጋጩ ፍላጎቶችና ፍትጊያዎች ፣ ወዘተ ... በመካከላቸው ስለሚኖሩ ከፊል ቅኝ ግዛቶቹ በማንኛቸውም የተፈጥሮና የኅብረተሰብ አካባቢ ሊገኙ ለሚችሉ የመሸጋገሪያ ዓይነቶች ጥሩ ምሳሌ ሊሆኑ የሚችሉ ናቸው ። ገንዘባዊ ወረት በማንኛውም የምጣኔ—ሀብትና የዓለም አቀፍ ግንኙነቶች(ከፍተኛና ወሣኝም ማለት ይቻላል)፤ ኃይል በመሆኑ ሙሉ የፖለቲካ ነጻነት ያላቸውን ሀገሮች እንኳን ሣይቀር በቁጥጥሩ ሥር አውሏል ፣ እያዋለም ነው ። ለዚህ ጥቂት ዝቅ ብለን ምሣሌ እንጠቅሣለን ። እርግጥ ገንዘባዊ ወራት በቁጥጥር ሥር ያዋለውን አገርና ሕዝብ የፖለቲካ ነጻነት ለመግፈፍ የሚ

ያስችል ሁናቴ ቢያጋጥመው ደስታው ነው ፤ ምክንያ ቱም ከፍተኛ ትርፍ ለመዛቅ « ያመቸዋልና » ነው ። በዚህ አንጻር የከፊል ቅኝ ግዛት አገሮች ለዚህ « ለመካከለኛ አቋም » ዓይነተኛ ምሣሌዎች ናቸው ። ሌላው የዓለም ክፍል ተካፋፍሎ በነበረበትና በገንዘባዊ ወረት ጊዜ እን ዚህን ግማሽ ነጻ የሆኑ አገሮች ለመያዝ የነበረው ትግል መራር የሆነ ነበር ።

ኢምፔሪያሊዝምና የቅኝ ግዛት ፖሊሲ ከካፒታሊ ዝም ዕድገት አስቀድሞ ፣ እንዲያውም ከካፒታሊዝምም በፊት ነበሩ ። በባሪያ ሥርዓት ላይ የተመሠረተችው ሮም የቅኝ ግዛት ፖሊሲንና ኢምፔሪያሊዝምን ታራምድ ነበር። ይሁንና በኅብረተሰብ — የምጣኔ — ሀብት አመሠራረት መካከል ያለውን መሠረታዊ ልዩነት ዝቅ የሚአደርግ ወይም ወደ ጎዳ የሚጥል « አጠቃላይ » የኢምፔሪያሊ ዝም ማብራሪያ በማያጠራጥር ሁኔታ « ታላቋ ሮማና ታላቋ ብሪታኒያን[82] » እንደማወዳደር ዓይነት ወደ ከንቱ ውሸት ወይም ወደፍጹም ጣም የለሽ ተራነት ነው የሚ አመራው ። የመጀመሪያው የካፒታሊዝም ደረጃ የቅኝ ግዛት ፖሊሲ እንኳን ከገንዘባዊ ወረት የቅኝ ግዛት ፖሊሲ ይለያል ። የመጨረሻው የካፒታሊዝም ደረጃ ዋነኛ ጠባዩ የታላላቅ ቀጣሪዎች ሞኖፖሊስቶች ማሕበራት ነው ። እን ዚህ ሞኖፖሊዎች የጥሬ ዕቃ ምንጮችን በቁጥጥራቸው ሥር በሚያደርጉበት ጊዜ ተጠናክረው ይደራጃሉ ፤ ዓለም አቀፍ የካፒታሊስት ኅብረቶች በእንዴት ያለ ጥበብ ተጻ ራሪዎቻቸውን የብረት ማዕድኖችን ፣ የዘይት ጉድጓዶ ችን ፣ ወዘተ.....በመግዛት እንዳይወዳደሯቸው ማናቸው ንም ጥረት እንደሚያደርጉ ተመልክተናል ። የቅኝ ግዛት ይዞታ ብቻ ነው ድንገት ከሚነሱ ተወዳዳሪዎች የመንግ ሥት ሞኖፖሊ ሕግ አውጥተው እራሳቸውን ለመከላከል

ከሚጥሩትም ጭምር ለሚያደርጉት ትግል ለሞኖፖሊዎቹ ሙተማመኛ የሚሆናቸው ። ካፒታሊዝም በይበልጥ እያደገ በሄደ መጠን ፥ የጥሬ ዕቃ እጥረት ይጨምራል ፥ በዓለም አካባቢ የጥሬ ዕቃ ምንጮችንም ለማግኘት የሚደረገው ውድድር እየተጠናከረ ይሄዳል ፥ ብሎም ቅኝ ግዛቶችን ለማግኘት የተፋፋመ ትግል ይደረጋል ።

« ለአንዳንዶች የማይታመን መስሎ ቢታይም በቅርቡ የወደፊት ጊዜ የከተማውንና የኢንዱስትሪውን አካባቢ ሕዝብ ዕድገት ከምግብ እጥረት ይልቅ የጥሬ ዕቃ እጥረት ሊገታው እንደሚችል ማረጋገጥ ይቻላል » ሲል ሺልደር ጽፏል ። ለምሳሌ ተመኑ እያደገ የሄደው የቲምበር እንጨት (ዛፍ) እጥረት እያደገ ነው ፥ የቆዳም እንዲሁ ፥ ለጨርቃ ጨርቅ ኢንዱስትሪም የሚያስፈልገው ጥሬ ዕቃ እጥረት እየጨመረ ነው ። «የአፈብራኪዎች ኅብረት በኢንዱስትሪና በእርሻ መካከል አንድ ሚዛናዊ ቦታ ለመፍጠር ጥረት እያደረጉ ናቸው ፥ ለዚህም በምሳሌነት ሊጠቀሱ የሚችሉት በ1904 ዓመተ ምህረት የተመሠረተው ዓለም አቀፍ የጥጥ አጠንጣኞች (ኮተን ስፒነርስ) ኅብረት ፌዴሬሽንና በተመሣሣይ መልክ በ1910 ዓመተ ምሕረት የተመሠረተው የአውሮፓውያን የተልባ አገዳ ቃጫ አጠንጣኞች (ፍላክስ ስፒነርስ) ፌዴሬሽን ናቸው[83] ።

እርግጥ የቡርዧ ጠጋኖች ከነዚህም መካከል በተለይ የጊዜያችን የኮትስኪ ተከታዮች ጥሬ ዕቃ ፥ « ውድና አዳገኛ » የሆነውን የቅኝ ግዛት ፖሊሲ ሳንከተል ፥ ከገበያ ለማግኘት « ይቻላል » በማለት እነዚህን ዕውነታዎች ለማቃለል ይጥራሉ ። ቀጥለውም ባጠቃላይ የእርሻ ሁኔታዎችን በማሻሻል ለገበያ የሚቀርበውን ጥሬ ዕቃ «በቀላሉ » በአያሌ ለማሳደግ « ይቻላል » ይላሉ ። የዚህ ዓይ

ነቱ የመከራከሪያ ሃሣብ ለኢምፔሪያሊዝም ይቅርታ እን ደመጠየቅና እሱንም በብሩህ ቀለም ቀብቶ እንደማቅረብ ይሆናል ። ምክንያቱም የካፒታሊዝምን የመጨረሻ ደረጃ ድኸውም የሞኖፖሊዎች መፈጠርን ዓይነተኛ ባሕርይ አያስታውስምና ፣ ነጻ ገበያ ቀስ በቀስ አንዱ ተረት እየሆነ ነው ፣ የሞኖፖሊ ሲንዲኬቶችና ትረስቶች ከቀን ወደቀን እያጠበቡት ስለመጡ «እንዲየው ዝምብሎ ስለሄደ» የእርሻ ሁኔ ታዎችን ማሻሻል ማለት የሰፊውን ሕዝብ የኑሮ ሁኔታ ማሻሻል ፣ ምንዳዕን ማሳደግ ፣ ትርፍን መቀነስ ማለት ይሆናል ። በስሜት የተገፋፉ ጠጋኞች የሃሣብ ነጸብራቅ ካልሆነ በስተቀር እንዴት አድርጎ ነው ማናቸውም ትረ ስት ለቅኝ ግዛት መዝመቱን ትቶ ለሰፊው ሕዝብ የኑሮ ሁኔታ ሊያስብ የሚችለው ?

ገንዘባዊ ወረት በጁ ያደረጋቸውን የጥሬ ዕቃ ምን ጮች ብቻ ሳይሆን ተጨማሪዎችንም ለማግበስበስ ይሯ ሯጣል ። ምክንያቱም የጊዜው የቴክኒክ ዕድገት በጣም ፈጣን በመሆኑና አዳዲስ ዘዴ ከተፈለሰፈና ከፍተኛ ወረት ከፈሰሰበት ዛሬ የማይጠቅመው መሬት ነገ ሊሻሻልና ጥቅም ሊሰጥ ስለሚችል (በዚህም አንጻር አንድ ትልቅ ባንክ ልዩ የመሐንዲስ ፣ የግብርና ጠበብት ወዘተ ፣ ለማሠማራት ስለሚችል) መሬት የሚሻሻልበትን አዳዲስ ዘዴዎች ሊያ ስቀይስ ይችላል ። ማዕድናትን ለማግኘት የሚደረገው አሠሣም ሆነ የጥሬ ዕቃዎች አመራረትና አጠቃቀም በተመሣሣይ መንገድ እንዲሻሻል ይደረጋል ፣ ወዘተ..... ስለዚህም ገንዘባዊ ወረት የተፅዕኖ ክልሉንና ያለውንም ግዛቱን ለማስፋፋት ጥረት የሚያደርግ መሆኑ የሚያጠ ራጥር አይሆንም ። ልክ ትረስቶች ያላቸውን ወረት ፣ ወደ ፊት የሚያስገኘውን ጥቅምና (ያለውን ሳይሆን) የሞኖ ፖሊን ተጨማሪ ውጤት በማሰብ ፣ በሁለትና በሶስት

እጅ እንደሚያሣድጉት ሁሉ ገንዘባዊ ወረትም ባጠቃላይ ባገኘው ዘዴ ፣ በየትም አካባቢ ማናቸውንም ዓይነት መሬት ፣«የወደፊት የጥሬ ዕቃ ምንጭነቱን» በማመን የመጨረሻውን ትራፊ መሬት ለመቀራመትም ሆነ የሌ ላውን ቅኝ ግዛት ለመንጠቅ ወይም የእነዚያን ቀድም ብለው የተከፋፈሉትን ግዛቶች እንደገና ለመከፋፈል ለሚ ደረገው ትግል ወደ ኋላ እንዳይቀር በመፍራት ለማጋበስ ከፍተኛ ጥረት ያደርጋል ።

የእንግሊዝ ካፒታሊስቶች በቅኝ ግዛታቸው ውስጥ የጥጥን ተክል ለማስፋፋት ከፍተኛ ጥረት ያደርጋሉ ፣ በግ ብፅ(በ1904 ለርሻ ከሚውለው 2,300,000 ሄክታር መሬት ውስጥ 600,000ው ወይንም ከአንድ አራተኛው በላይ ለጥጥ ተክል ውሏል ።) ሩሲያውያንም በቅኝ ግዛታቸው በቱርክስታን ተመሣሣይ ድርጊት ይፈጽማሉ ፣ ምክን ያቱም በዚህ መንገድ የውጪ ተወዳዳሪዎቻቸውን ለማ ሸነፍ ፣ የጥሬ ዕቃዎችን ምንጮች በሞኖፖሊዎቻቸው ውስጥ ለማጠቃለልና ሁሉም የጥጥ አመራረት በአንድ የባ ለቤት ቡድን ሥር « እንዲጣመርና » እንዲደልብ አድር ገው ይበልጥ ቁጠባና ትርፍ የሞላበት የጨርቃ ጨርቅ ትረስት ለመፍጠር ይችላሉ ።

በቅኝ ግዛት ውስጥ ባለው ገበያ የሞኖፖሊ ዘዴዎችን ከሥራ ላይ ማዋል (እንዲያውም አንዳንድ ጊዜ አማራጭ የሌለው በሥራ ላይ ለማዋል የሚቻለው ዘዴ እሱ ብቻ ይሆናል)፤ ይህም ውድድርን ለማስወገድ ፣ የጥሬ ዕቃ ምን ጮችን ለማረጋገጥና አስፈላጊውን«የግንኙነቶችን » ፣ ወዘተ . . . ደህንነት ለመጠበቅ ስለሚቻል ወረትን ወደውጭ መላክ ቅኝ ግዛት የመያዝ ጉጉት ያሳድራል ።

በገንዘባዊ ወረት መሠረት ላይ የሚያድገው ምግኔ— ሀብታዊ ያልሆነው ላዕላይ መዋቅር ማለትም ፖለቲካ

ውና ርዕዮተ ዓለሙ ቅኝ ግዛቶችን ለመያዝ ይገፋፋል ። «ገንዘባዊ ወረት ነጻነትን ሳይሆን ገዢነትን ነው የሚሻው» ሲል ሂልፈርዲንግ በትክክል ተናግሮታል ። ከፍ ብሎ የተጠቀሰውን የሲሲል ሮድስን* ሃሳብ በማጠናከርና በማዳበር አንድ የፈረንሳይ ጸሐፊ ሲጽፍ በዘመናዊ ቅኝ ግዛት ፖሊሲ ውስጥ ምጣኔ—ሀብታዊ መንስኤዎች ብቻ ሳይሆኑ ሕብረተሰባዊ መንስኤዎችም መታከል እንዳለ ባቸው አሳስቧል ። «በሰፊው ሠርቶ አደር ብቻ ሳይሆን በመካከለኛውም መደብ እያደገ የመጣው የኑሮ ውስብስ ብነትና ክብደቱ እየጨመረ የሄደው ቅብጥብጥነት ፣ ብስጭትና ጥላቻ እየተከማቸ የጥንት ሥልጣን በነበራ ቸው ሀገሮች ሁሉ ለኅብረተሰብ ሥርዓት እንቅፋት እየ ሆነ ነው ። በሀገር ቤት ንቅናቄው እንዳይፈነዳ ለማድረግ ይህን ከአንድ መደብ የሚወረወር ኃይል ወደ ውጭ ሀገ ሮች ተልኮ ሥራ ላይ እንዲውል ማድረግ ይኖርበታል[84] ።»

በከፍተኛው የታሪክ ዘመን ስላለው የካፒታሊስት ኢምፔሪያሊዝም የቅኝ ግዛት ፖሊሲ የምንነጋገር ስለ ሆነ ገንዘባዊ ስልጣንና ዓለምን በምጣኔ ሀብትና በፖለቲካ ለመከፋፈል መታገል ዋና ተግባሩ የሆነው የውጪ ፖሊ ሲው ፣ ለመንግሥት የአንዱ ለአንዱ ጥገኛ መሆን በር ካታ የመሸጋገሪያ ቅርጾች እንደሚሰጥ መገንዘብ አለብን። ሁለቱ ዋና ዋና ወገኖች ማለት ቅኝ ግዛቶችና ቅኝ ገዢዎች ብቻ ሳይሆኑ በፖለቲካ ነጻ ሆነው በገንዘብና በዲፕሎማ ቲክ መረብ ጥገኝነት ውስጥ ተይዘው የሚገኙትም የዚህ ከፍተኛ የታሪክ ዘመን ዓይነተኛ ገጽታዎች ናቸው ። ስለከፊል ቅኝ ግዛት ጥገኝነት ከፍ ሲል ገልጸናል ። ሌላም ምሣሌ ቢያስፈልግ አርጀንቲናን ማቅረብ ይቻላል ።

« ደቡብ አሜሪካ በተለይም አርጀንቲና » ይላል ሹልዝ ጋቨርኒትዝ ስለ እንግሊዝ ኢምፔሪያሊዝም በጻፈው

ጽሑፍ ውስጥ «ልክ የእንግሊዝ የንግድ ቅኝነት ሊያ ሰኛት የሚያስችል ያህል በለንደን ላይ የገንዘብ ጥገኛ ነች[85]» ። *** በ1909 ዓ. ም. በቦነስ አይረስ የአውስ ትርያና የሀንጋሪ ቆንሲል የሰጠውን ዘገባ መሠረት በማድረግ ሼልደር ፣ እንግሊዝ በአርጀንቲና ውስጥ የነበ ራት ወረት 8,750 ሚሊዮን ፍራንክ እንደነበር ይገም ታል ። የእንግሊዝ ገንዘባዊ ወረት /እና የልብ "ወዳጁ" ዲፕሎማሲ) ከአርጀንቲና ቡርዣዎች ጋር ማለትም የሀገሪ ቱን ምጣኔ—ሀብታዊና ፖለቲካዊ ሕይወት ከሚቆጣ ጠሩት ጋር ምን ዓይነት የጠነከረ ግንኙነት እንነበረው መገመት አያዳግትም ።

ከፖለቲካ ነጻነት ጋር ተያይዞ የሚገኝ ለየት ያለ የገንዘብና የዲፕሎማቲክ ጥገኝነት በፖርቱጋል የቀረበው ነው ። ፖርቱጋል አንድ የግዛት አንድነቷ የታወቀላት ነጻ አገር ናት ፣ ይሁን እንጂ ከስፔይን መተካት ጦርነት ጀምሮ (1701—14) ከሁለት መቶ ዓመታት በላይ ለሚሆን ዘመን በእንግሊዝ ሞግዚትነት ስር ነበረች ። ታላቋ ብሪታንያ ፖርቱ ጋልንና ሌሎቹን ቅኝ ግዛቶችዋን ከተቀናቃኞቿ ከፈረን ሣይና ከስፔይን ጋር ለምታደርገው ጦርነት አቋሟን ለማ ጠናከር ፣ ትጠብቃቸው ነበር ። በምትኩም ታላቋ ብሪታ ንያ የንግድ መብቶችን ፣ ዕቃዎችን ወደ አገር የማስገባ ትና በተለይም ካፒታሏን ወደ ፖርቹጋልና የፓርቱጋል ቅኝ ግዛቶች ወደ ሆኑ ሀገሮች ለመላክ የተለየ ሁኔታን በፖርቱጋል ወደቦችና ደሴቶች የመጠቀም ፣ በቴሌግራፍ ሽቦዎች የመገልገል መብት፤ ወዘተ... አግኝታለች[86]።* የዚህ ዓይነት ግንኙነቶች በታላላቅና በትናንሽ መንግሥታት መካከል ለብዙ ጊዜ ነበሩ። ይሁንና በካፒታሊስት ኢምፔ ሪያሊዝም ዘመን (ኡፓክ) አጠቃላይ ሥርአትና ከአጠቃላይ «አለምን የመከፋፈል» ግንኙነት አንደኛውን ክፍል ይመ

ሠርቱና የአለም ገንዘባዊ ወረት ሰንሰለት ዓይነት አሠራር ማገናኛ ይሆናሉ ።

የዓለም መከፋፈል ጥያቄን ለመፈጸም በተጨማሪ የሚከተለውን ለማለት እፈልጋለሁ ። ይህ ጥያቄ በይፋና በተረጋገጠ መልክ የተነሣው ከስፓኝና አሜሪካ ጦርነት በኋላ በአሜሪካን ሥነ ጽሑፍ (ሊትሬቸር) ብቻ አይደለም፤ ወይንም በአሥራ ዘጠነኛው ክፍለ ዘመን መጨረሻና በሃያኛው ክፍለ ዘመን መጀመሪያ ላይ ተደርጎ ከነበረው የአንግሎቦር ጦርነት በኋላ በእንግሊዝ ሥነ ጽሑፍ ላይ ብቻም አይደለም ፤ የእግሊዝን ኢምፔሪያሊዝም በታላቅ ቅናት ትከታተል የነበረው የጀርመን ሥነ ጽሑፍም ለዚህ ሐቅ ትክክለኛውን ቦታ አልሰጠውም ። ከቡርዧ አመለካከት አንጻር ሲታይ ሊታሰብ በሚቻል መጠን ሰፋ ባለና ግልጽ በሆነ አኳኋን ይህ ጥያቄ በፈረንሣይ የቡርዧ ሥነ ጽሑፉም ተነስቷል ። « ፖለቲካዊና ኅብረተሰብአዊ ችግሮች በአሥራ ዘጠነኛው ክፍለ ዘመን መጨረሻ ላይ» በሚለው መጽሐፉ ውስጥ «የሀያላን መንግስታትና የዓለም መከፋፈል » በሚለው ምዕራፍ ውስጥ ከዚህ ቀጥሎ ያለውን ሃሣብ ያሠፈረውን ታሪክ ጸሐፊውን ድያውልትን ልጥቀስ :-« ባለፉት ጥቂት ዓመታት ውስጥ የዓለም ነጻ ግዛቶች፣ከቻይና በስተቀር፣በአውሮፓና በሰሜን አሜሪካን ኃያላኖች ተይዘው ነበር ። ይህም አያሌ ግጭቶችንና የተፅእኖ ክልሎችን (ስፌርስ ኦፍ ኢንፍሉዌንስ) ከአንዱ ወደ አንዱ ይዞታ እንዲሸጋገሩ አድርጓል ። እነዚህም በተራቸው በቅርብ የወደፊት ጊዜ የሚደርሱት የሁኔታዎች መገለባበጥን (አፕሂቫል) ያንፀባርቃሉ ። ምክንያቱም መጣደፍ አስፈልጓልና ። እስካሁን ድረስ ለራሳቸው መጠቀሚያ መንገዳቸውን ያላዘጋጁት

አገሮች በሚቀጥለው ምዕተ ዓመት (ማለትም በ20ኛው) ይበልጥ የዓለም አይነተኛ ጠባይ በሚሆነው ፣ ድርሻቸውን በማያገኙበትና ፍጹም በሠፊው ብዝበዛ ላይ በማይሳተፉበት አደጋ ውስጥ ይገባሉ ። ስለዚህ ነው መላ አውሮፓና አሜሪካ ከጥቂት ጊዜ ወዲህ የአሥራ ዘጠነኛው ክፍለ ዘመን ሊታወስ በሚገባው ባሕርይ ፣ በኢምፔሪያሊዝም የቅኝ ግዛት መስፋፋት ትኩሣት ሕመም የተለከፉት ፣ «ደራሲውም በመቀጠል » በዚህ የዓለም መቀረማመት ፤ በዚህ ቁጣ በተመላበት የዓለምን ከፍተኛ የገበያ ቦታና የተደበቀ ሃብት አደን ፣ በአሥራ ዘጠነኛው ክፍለ ዘመን የተመሠረቱት ግዛቶች አቅም አውሮፓ ሲመሠረት ከነበረው አቅም ጋር አይመጣጠንም ። የአውሮፓ ኃያላን መንግሥስታት የራስዋም የወደፊት ዕድል አጋፋሪዎች ፣ በዓለም ላይ የተመጣጠነ የኃይል ሚዛን የላቸውም ። ስለሆነም አንድ የቅኝ ገዢ ኃያል ፣ ከግምት ውጪ እስከአሁን ግምት ሊሰጠው ያልተቻለውን ሀብት ለመቆጣጠር ያለው ተስፋ የእያንዳንዱን የአውሮፓ ኃያላን ኃይል ይጸረራል ። የቅኝ ግዛቱ ጥያቄ (ኢምፔሪያሊዝም ሊባል ይቻላል) የራሱ የአውሮፓን የፖለቲካ ሁኔታ እንደለወጠው ሁሉ በበለጠ ይለውጣቸዋል[87] ።»* ሲል ድሪያውልት አትቷል ።

ም ዕ ራ ፍ ሰ ባ ት

# ኢምፔሪያሊዝም እንደልዩ የካፒታሊዝም ደረጃ

ቀደም ሲል ስለ ኢምፔሪያሊዝም ያነሣናቸውን ሃሳቦች ለማጠቃለል እንሞክር።ኢምፔሪያሊዝም የመጣው

ካፒታሊዝም ባጠቃላይ መሠረታዊ ጠባዮቹን በመያዝ በማደጉ ነው ። ይሁን እንጂ ካፒታሊዝም ካፒታሊስት ኢምፔሪያሊዝም የሆነው ፣ አንዳንድ መሠረታዊ ጠባዮቹ ወደ ተቃራኒያቸው መለወጥ ሲጀምሩ ፣ የከፍተኛው ታሪካዊ ወቅት ባህርያት ከካፒታሊዝም ወደ ከፍተኛው የኅብረተሰብና የኤኮኖሚ ሥርዓት የመሸጋገር ቅርጽ ሲያወጡና ራሳቸውንም በየአካባቢው ብቅ ብቅ ማድረግ ሲጀምሩ ፣ በአንድ በተወሰነ ከፍተኛ የዕድገት ደረጃው ነው ። በዚህ ሂደት በምጣኔ ሀብት አንጻር ዋነኛው የታየው ለውጥ የካፒታሊስት ነጻ ውድድር በካፒታሊስት ሞኖፖሊ መተካት ነው ። ነጻ ውድድር የካፒታሊዝም መሠረታዊ ባሕርይ ሲሆን ለሸቀጥ ምርት ግን አጠቃላይ ባሕርዩ ነው ። ሞኖፖሊ የነጻ ውድድር ቀጥተኛ ተቃራኒ ነው ። ይሁን እንጂ ነጻ ውድድር ትንንሽ ኢንዱስትሪዎችን እያጠፋ በትልልቆች እየተካ ፣ ትልልቅ ኢንዱስትሪዎችንም ቢሆን በበለጠ ትልልቅ ኢንዱስትሪ እየተካ እና ምርትና ወረትን በከፍተኛ ደረጃ እያከማቸ ወደ ሞኖፖሊነት ሲለወጥ በአይናችን አይተናል ። ስለሆነም ካርቴሎች ፣ ሲንዲኬቶችና ትረስቶች ፣ በሺህ ሚሊዮን የሚቆጠሩ ብሮች የያዙ የበርካታ ባንኮችን ካፒታል ከነሱ ጋር እያዋሀዱ ሲያድጉ ተመልክተናል ። በነጻ ውድድር ውስጥ ተፈጥረው ያደጉት ሞኖፖሊዎች ነጻ ውድድርን በማጥፋት ፈንታ ጐን ለጐንና ከበላዩ ሆነው የተፋፋመ ቅራኔ ፣ ፍትጊያና ግጭት በመፍጠር ሁኔታውን ያመቻቻሉ ። ሞኖፖሊ ከካፒታሊዝም ወደ አንድ ከፍተኛ ሥርዓት መሸጋገሪያ ነው ።

ለኢምፔሪያሊዝም በጣም አጭር የሆነ ትርጉም መስጠት ቢያስፈልግ ኢምፔሪያሊዝም የካፒታሊዝም የሞኖፖሊ ደረጃ ነው ማለት እንችላለን ። የዚህ ዓይነቱ ትር

ጉም በጣም ጠቃሚ የሆኑትን ሁለት ባሕርዮችን በው ስጡ ይይዛል ። በመጀመሪያ ደረጃ ገንዘባዊ ወረት ማለ ትም የጥቂት ታላላቅ ሞኖፖሊስት ባንኮች ካፒታል ከሞ ኖፖሊስት የኢንዱስትሪዎች ኀብረቶች ጋር ሲዋሃድ የሚ ገኘው ወረት የሞኖፖሊ ውጤት መሆኑን ፣ በሁለተኛ ደረጃ ደግሞ ቀደም ብለው በአንዳንድ ካፒታሊስት ሀገ ሮች ያልተያዙ ግዛቶችን ፣ ያለአንዳች ችግር ፣ በመሰብ ሰብ እየተስፋፉ ከመጣው የቅኝ ግዛት ፖሊሲ ወደ ሙሉ በሙሉ የተከፋፈለችውን ዓለም በሞኖፖሊ የመያዝ የቅኝ ግዛት ፖሊሲ መሸጋገሪያው የዓለም መሸጋገሪያው የዓ ለም መከፋፈል መሆኑ ናቸው ።

ትርጉሞቹ አጭጭር ናቸው ። ዋና ዋና ነጥቦችን አጠ ቃለው በመያዛቸው ጠቃሚ ቢሆኑም ፣ ትርጉም የተደረ ገለትን ክስተት የተለየ ጥቅም ያላቸውን ባሕርያት ከነሱ ለመረዳት እንድንችል ስለማያስገድዱ የተሟሉ ናቸው ማለት አይቻልም ። ስለዚህም የአንድን ክስተት በመላ የዕድገት ጊዜው የሚያጋጥሙትን ሁሉንም የተያያዙ ሂደቶች በአጠቃላይ ትርጉሞች አቅፈው ስለሚይዙ የት ርጉሞችን ሁኔታዊና አንጻራዊ ዋጋ ሳንዘነጋ ፣ አምስቱን መሠረታዊ ባሕርዮቹን አጠቃሎ የሚይዘውን የኢምፔ ሪያሊዝም ትርጉም እንደሚከተለው እናቀርባለን ።

1. የምርትና የወረት ድልበት ወደ ከፍተኛ ደረጃ በማ ደጉ በምጣኔ ሀብት ሕይወት ውስጥ ወሣኝ ሚና ለሚጫወተው ለሞኖፖሊ መፈጠር ምክ ንያት መሆን ፣

2. የባንክ ካፒታልና የኢንዱስትሪ ካፒታል ተዋ ሀደው በዚህም መሠረት « ገንዘባዊ ወረት » ብሎም ገንዘባዊ ስልጣን ሲፈጠር ፤

3. የወረት ወደ ውጪ መላክ ከሸቀጦች ወደ ውጪ መላክ ጋር ሲነጻጸር ከፍተኛ ግምት ሲያገኝ ፤

4. ዓለምን በመካከላቸው የሚቀራመቱ ዓለም አቀፍ የሞኖፖሊስት ካፒታሊስት ኅብረቶች መመስረት ፤

5. ታላላቅ የካፒታሊስት ኃያላን መንግሥታት ዓለምን በግዛት መከፋፈላቸው መጠናቀቁ ናቸው ።

ኢምፔሪያሊዝም በአንድ የዕድገት ደረጃ የሞኖፖሊዎችና የገንዘባዊ ወረት የበላይነት የሚታይበት ፥ የካፒታል ወደ ውጪ መላክ ከፍተኛ ጥቅም መሆኑ የሚታወቅበት ፥ ዓለም አቀፍ ትረስቶች ዓለምን መከፋፈል የጀመሩበት ፤ ታላላቅ ካፒታሊስት ኃያላን መንግሥታት ዓለምን በግዛት ተከፋፍለው ያበቁበት ፥ ካፒታሊዝም ነው ።

ብቸኛና መሠረታዊ የሆነውን የኤኮኖሚ አመለካከት ብቻ ሣይሆን (ከላይ የተሰጠው ትርጉም በዚህ ብቻ ስለሚያተኩር)ካጠቃላዩ ካፒታሊዝም የዚህኛውን ካፒታሊዝም ታሪካዊ አቋም ወይንም በኢምፔሪያሊዝምና በሠርቶ አደሩ ንቅናቄ ሁለት አዝማሚያዎች መካከል ያለውን ግንኙነት ስንመለከት ኢምፔሪያሊዝም ለየት ያለ ትርጉም ሲይዝና መያዝም እንዳለበት እናያለን ። እዚህ ላይ መታወስ ያለበት ነገር ቢኖር ኢምፔሪያሊዝም ፥ ከላይ በተሰጠው ትርጉም መሠረት ፥ በካፒታሊዝም ዕድገት ለየት ያለውን ደረጃ እንደሚያመለክት አያጠራጥርም ። አንባቢው ስለ ኢምፔሪያሊዝም በደንብ የተጠናከረ ሀሣብ እንዲኖረው ስል ስለ የመጨረሻው የካፒታሊስት ምጣኔ ሀብት የዕድገት ደረጃ በተለይ የማያከራክሩትን ሐቆች አምነው የሚቀበሉትን የቡርዧ ኤኮኖሚስቶች ሆን ብዬ ጠቅሻለሁ ። ለዚሁ ዓላማ ስል የባንክ ወረት፤ወዘተ ምን

ያሀል እንዳደገና ከመጠን ወደ አይነት የተለወጠ የአ ደገ ካፒታሊዝም በኢምፔሪያሊዝም እንደ ተገለጸ ሊያሣዩ የሚችሉትን ዝርዝር እስታትስቲኮች ጠቅሻለሁ ። በተ ፈጥሮና በኅብረተሰብ ዕድገት ውስጥ ያሉ መስመሮች ከልሎች ተለዋዋጭና ልማዳዊ (ኮንቬንሺናል) በመሆና ቸው ለምሳሌ ኢምፔሪያሊዝም « በትክክል» በዚህ ዓመት ወይንም በነዚህ አሥር ዓመታት ውስጥ ተመሠረተ ብሎ መከራከር የሚያሣፍር መሆኑ መነገር ያለበት አይመስ ለኝም ።

ለኢምፔሪያሊዝም ትርጉም በመስጠቱ ጉዳይ ላይ የሆነ እንደሆነ በ1889ና በ1914 ዓ. ም. መካከል የሃያ አምስቱ ዓመታት ሁለተኛው ኢንተርናሲዮናል በመባል በሚታወቀው ከፍተኛ የታሪክ ወቅት ዋነኛ የማርክሲ ስት ንድፈ ሀሣባዊ(ቲዎረቲሺያን) ከነበረው ከካርል ኮት ስኪ ጋር በቅድሚያ የሃሣብ ቅራኔ እናነሣለን ። ኮትስኪ በ1915 ዓመተ ምሕረት እንዲያውም በኅዳር 1914 ዓ.ም. ስለ ኢምፔሪያሊዝም በሠጠነው ትርጉም ውስጥ የተጋለ ጡትን መሠረተ ሃሣቦች በጣም በተጠናከረ አቋም ዋጋ ሊያሣጣቸው ቅዋሚውንም እንዲህ ሲል ነበር ያቀረበው። ኢምፔሪያሊዝም እንደ አንድ የኤኮኖሚ ደረጃ ሣይሆን እንደ ፖሊሲ ፥ እንደ አንድ የተወሰነ የገንዘባዊ ወረት ፖሊሲ ሆኖ « መታየት » አለበት ፥ ኢምፔሪያሊዝም «ከአሁኑ ጊዜ ካፒታሊዝም » «ጋር ተመሳስሎ » መታየት የለበትም ፥ ኢምፔሪያሊዝም « የጊዜው ካፒታሊዝም ጠቅላላ ክስተቶች » ማለትም ካርቴሎች ፥ ከለላ ፥ የባለገን ዘቦች የበላይነት ፥ የቅኝ ግዛት ፖሊሲ ነው ብለን ከተረ ዳን ኢምፔሪያሊዝም ለካፒታሊዝም የማስፈለጉ ጥያቄ ድድብ ያለ ያንኑ ሃሣብ መደጋገም ይሆናል ። ምክንያቱም ይህ ከሆነ«ኢምፔሪያሊዝም ለካፒታሊዝም በጣም አስ

በጣም አስፈላጊ ሊሆን ነው ፡ » ወ. ዘ. ተ. . . . ። የኮትስኪን ሀሣብ ለማቅረብ ዓይነተኛው መንገድ ለኢምፔሪያሊዝም የሰጠውን ትርጉም መጥቀስ ነው ። የሱ ትርጉም እኔ ካቀረብኩት ሀሣብ ፍሬ ነገር ጋር ሙሉ በሙሉ ይቃረናልና ። ( የዚህም ምክንያት ተመሣሣይ ሀሳቦችን ሲያስተጋቡ ከነበሩት የጀርመን ማርክሲስቶች አምባ ለብዙ ዓመታት ሲቀርጹ ስለነበርና እነዚህ ቅዋሚዎች ለኮትስኪ እንደ አንድ የማርክሲዝም ጠቅላላ ዝንባሌ (ቴንደንሲ) መስለው ይታዩት ስለነበረ) ። የኮትስኪ ትርጉም የሚከተለው ነው ።

« ኢምፔሪያሊዝም በከፍተኛ ደረጃ ያደገ የኢንዱስትሪ ካፒታሊዝም ውጤት ነው ። እያንዳንዱ ካፒታሊስት መንግሥት ምንም ዓይነት የብሔር ሕዝቦች ይኑርበት ሳይለይ ማንኛውንም የመሬት ግዛት ለራሱ በመውሰድ ወይንም በቁጥጥሩ ሥር በማድረግ ጥረት እያደረገ የሚኖር ነው[88] ። *

ይህ ትርጉም ረብ የሌለው ነው ። ምክንያቱም የብሔርን ጥያቄ (ምንም እንኳን ይህ ጥያቄ ከኢምፔሪያሊዝም ጋር ባለው ግንኙነትም ሆነ ራሱን ችሎ በጣም ጠቃሚ ቢሆንም) ከአንድ አቅጣጫ በማየትና በዘፈቀደ ነጥሎ ስለሚያይ ይህን ጥያቄ ሌሎችን መንግሥታት በሚጠቀልሉ መንግሥታት ውስጥ ከሚገኝ ኢንዱስትሪያል ወረት ጋር ትክክል ባልሆነ መንገድና በዘፈቀደ ስለሚያያዝ የገጠር አካባቢዎችንም ትክክል ባልሆነ መንገድና በዘፈቀደ ማጠቃለልን ግምባር ቀደም ስለሚያደርግ ነው ።

ኢምፔሪያሊዝም የግዛት ማስፋፋት ጥረት ነው ፤ ይህ ነው የኮትስኪ ትርጉም የፖለቲካው ክፍል የያዘው ። ምክንያቱም ኢምፔሪያሊዝም በአጠቃላይ በፖለቲካው በኩል

ለቅልበሳና ለአመጽ የሚጥር በመሆኑ ይህ ትክክል ነው ፤ ሆኖም የተሟላ አይደለም ። ለጊዜው ግን ኮትስኪ በትርጉሙ ውስጥ በጠቀሰው በምጣኔ ሀብቱ አንጻር ላይ እናተኩራለን ። በኮትስኪ ትርጉም ውስጥ ያለው ስህተት ፍጥጥ ብሎ ይታያል ። የኢምፔሪያሊዝም ዓይነተኛ ባሕርይ ገንዘባዊ ወረት እንጂ ኢንዱስትሪያላዊ ወረት አይደ ደለም ። ከ1880 ዓ. ም. ወዲህ በፈረንሣይ አገር ለግዛት መስፋፋት ፖሊሲ ከፍተኛ መጧጧፍ ያስከተለው የኢን ዱስትሪያዊ ወረት መዳከምና የገንዘባዊ ወረት በተለመደ ፍጥነት ማደግና መስፋፋት መሆኑ ድንገት የደረሰ ነገር አልነበረም ። የኢምፔሪያሊዝም ዓይነተኛ ጠባይ ያገኘ ውን የገጠር አካባቢ መውሰድ ብቻ ሳይሆን በከፍተኛ ደረጃ በኢንዱስትሪ የበለጸጉትንም አገሮች ጭምር ማጠ ቃለል ነበር ። (የጀርመን ለቤልጅግ መቋመጥ ፥ የፈረንሣይ ለሉሬይን መስገብገብ ) ። ምክንያቱም ፥

1. የዓለም ሙሉ በሙሉ የመከፋፈል ሐቅ የእን ደገና ክፍፍሏን ለሚፈልጉ አገሮች ያገኙትን ግ ዛት ለመያዝ ስለሚያስገድዳቸው ፤

2. በጣም ዓይነተኛ የሆነው የኢምፔሪያሊዝም ጠ ባይ ለተፅዕኖ ትግል የሚደረግ የታላላቅ ኃያላን መንግሥታት የመቀናቀን ጥረት ነው ። ይህም ማለት ለተጨማሪ ግዛት የሚስገበገቡት በመስ ፋፋት ፍላጎት ላይ በመመስረት ብቻ ሳይሆን ይበልጡን ጊዜ ተፅዕኖ የሚያደረባቸውን መንግ ሥት ለማዳከም ነበር ። (ጀርመን ፥ ኢንግሊዝን ለመውጋት እንድትችል በተለይ ቤልጅግ ለጠቃ ሚ የጦር ሠፈር አስፈላጊ ናት ፥ እንግሊዝ ጀር መንን ለመውረር ባግዳድን ለጦር ሠፈርነት ትፈ ልጋለች ወ. ዘ. ተ . . . )

ኮትስኪ ለሱ በሚገባው መንገድ « ለኢምፔሪያሊ ዝም » ጥርት ያለ የፖለቲካ ትርጉም ሰጥተውታል በማ ለት ደጋግሞ በተለይ የእንግሊዝ ጸሐፊዎችን ይጠቅሣል ። በ1902 ዓ. ም. የታተመውን ኢምፔሪያሊዝም የሚለውን የእንግሊዙን ጸሐፊ የሆብሰንን ጽሑፍ ብንመለከት የሚ ከተለውን እናገኛለን ፦—

« አዲሱ ኢምፔሪያሊዝም ከቀድሞው የሚለየው ፣ መጀመሪያ የአንድን ግዛት በተናጠል ለማደግ ያለውን ምኞት እያንዳንዳቸው በተመሣሣይ ለፖለቲካ ኃያልነትና ለምጣኔ ሀብት ጥቅም በሚወዳደሩ ግዛቶች ንድፈ ሃሣብና ተግባር በመተካት ፣ ሁለተኛ ደግሞ በገንዘባዊ ተፅዕኖ ወይንም ለንግድ ጥቅም ከፍተኛ ወጪ በማድረግ ነው ። »[89]

ከዚህም ኮትስኪ የእንግሊዝ ጸሐፊዎችን ጠቀስኩ የሚለው (የእንግሊዝ ኢምፔሪያሊስቶችን መደዳውን ወይ ንም ለኢምፔሪያሊዝም ታጥቀው ጥብቅና የቆሙትን ማለ ቱ ካልሆነ በስተቀር) በፍጹም ስህተት ነው ። ኮትስኪ ለማርክሲዝም ነው የቆምኩት እያለ ቢለፍፍም ፣ እንደ እውነቱ ኪሆን በይበልጥ « ታሪካዊ ተጨባጭነት » ያላ ቸውን ሁለት የኢምፔሪያሊዝም ገጽታዎች በትክክል ካቀረበው የሕብረተሰብ ለዘብተኛው ሆብሰን ጋር ሲወ ዳደር አንድ እርምጃ ወደ ኋላ ሲራመድ ይታያል (የኮት ፤ ስኪ ታሪካዊ ተጨባጭነት ትርጉም ፌዝ ነው ። !!) እነኝህም

1. በአያሌ ኢምፔሪያሊዝሞች መካከል ያለው ውድድር እና
2. የባለገንዘቦች በነጋዴዎች ላይ የበላይ መሆን ነው ። በኢንዱስትሪ የበለጸጉ አገሮች ለእርሻ አመ ችነት ያላቸውን አገሮች የማጠቃለል ጉዳይ ቢሆን ኖሮ ጥያቄው የታላላቅ ነጋዴዎች ሚና ግምባር ቀደም ሥፍራ ይይዝ ነበር ።

የኮትስኪ ትርጉም ስህተትኛና ኢማርክሲስት የሆነ ብቻ አይደለም ። ለማርክሳዊ ንድፈ ሃሳብና ለማርክሲ ስት ተግባር ከመጀመሪያ እስከ መጨረሻ ቅራኔን ለሚያ ሣየው ያመለካከት ሥርዓት በመሠረትነት ያገለግላል ። ይህንን በሌላ ጊዜ እመለስበታለሁ ። የካፒታሊዝም የመ ጨረሻ ዕድገት ደረጃ ኢምፔሪያሊዝም ተብሎ ይጠራ ወይንም የገንዘባዊ ወረት ደረጃ ይባል የሚለው ኮትስኪ ያነሳው የቃላት ንትርክ ፋይዳ የለውም ። እንደፈለከ ጥራው ምንም ለውጥ አያመጣም ። የጉዳዩ ፍሬ ነገር ኮትስኪ የኢምፔሪያሊዝምን ፖለቲካ ከምጣኔ ሀብቱ ገን ጥሎ ይመለከታል ፤ የግዛት ማጠቃለል በገንዘባዊ ወረት « የተመረጠ » ፖሊሲ ነው ከማለቱም በላይ በዚሁ በገን ዘባዊ ወረት መሠረት ላይ ሊከሰት ይችላል የሚለውን ሌላ የቡርዧ ፖሊሲ በተቃራኒው ያስቀምጣል ። ይህም የምጣኔ ሀብት ሞኖፖሊዎች ፤ ሞኖፖላዊ አመጻዊ ፣ ግዛት አስፋፊ ካልሆኑ የፖለቲካ ዘዴዎች ጋር በአንድነት ይራ መዳሉ ማለት ነው ። ይህም በዚሁ በገንዘባዊ ወረት ታሪ ካዊ ወቅት የተጠናቀቀው ብሎም በአሁኑ ጊዜ ልዩ ቅርጽ የያዘው ለታላላቅ ካፒታሊስት መንግሥታት ውድድር መሠረት የሆነው የዓለም በግዛት መከፋፈል ኢምፔ ሪያሊስት ካልሆነ ፖሊሲ ጋር በአንድነት ይራመዳል ማለት ነው ። ውጤቱም የካፒታሊዝምን የመጨረሻ የዕድገት ደረጃ ጠላቅ ያሉ ቅራኔዎችን ጠለቅ ብሎ በመ ተንተን ፈንታ እነሱን ማዶልዶምና በቁንጽል ማቅረብ ይሆናል ። የዚህም ውጤት ማርክሲዝም ሣይሆን የቡር ርዧ ጠጋኝነት ነው ።

ኮትስኪ ከጀርመኑ የኢምፔሪያሊዝምንና የግዛት ማስ ፋት ተናሳሂ (አጉብዳጅ) ከሆነው ከኩኖው በጠባብ አመለካከትና ሀፍረተቢስ በሆነ መንገድ ኢምፔሪያሊ

ዝም የጊዜው ካፒታሊዝም ነው እያለ ከሚያቀርበው ጋር ቅራኔ ላይ ወድቋል ። ኩኖው በተጨማሪም የካፒታሊዝም ዕድገት የማይቀርና ተራማጅ ነው ፣ ስለዚህ ኢምፔሪያሊ ዝም ተራማጅ ነው ፣ ስለሆነም ከፊቱ ተንበርክከን ልና መልከው ይገባናል ይላል ። ይኸ ከ1894 እስከ 1Ɛ95 ዓ. ም. ናሮድኒኮች ስለሩሲያ ማርክሲስቶች ያቀረቡትን የማ ጥላሊያና የተጋነነ ጽሁፍ ይመስላልና ። ናሮድኒኮች ፣ ማር ክሲስቶች ካፒታሊዝም በሩሲያ ውስጥ የማይቀር ነው ፤ ተራማጅ ነው ብለው የሚሉ ከሆነ አንድ መናኸሪያ ከፍተው ካፒታሊዝምን ያስቀምጡልን ። ኮትስኪ ለኩ ኖው የሚሰጠው መልስ እንደሚከተለው ነው ፣ ኢምፔ ያሊዝም የጊዜያችን ካፒታሊዝም አይደለም ፣ የጊዜያችን ካፒታሊዝም ፖሊሲ አንድኛው ገጽ ብቻ ነው ። ይህንንም ፖሊሲ ልንዋጋው እንችላለን ፣ እንዋጋለን ፤ ኢምፔሪያሊ ሊዝምን የግዛት መስፋፋት ወ. ዘ. ተ. እንዋጋለን ።

የኮትስኪ መልስ ሐቀኛ ይመስላል ፣ ይሁን እንጂ ውጤቱ በጣም በብልሃት የቀረበና የተሸፋፈነ (ብሎም በ ጣም አደገኛ) ከኢምፔሪያሊዝም ጋር ለእርቅ የሚጋብዝ ፣ ምክንያቱም የትረስቶችንና የባንኮችን የምጣኔ ሀብት መሠ ረት ስንነካ እነሱን መዋጋት የዋህና ደግ በመሆን መንገድ ሃይማኖታዊ የሆነ ምኞትን መግለጽ ፣ ቅልጥ ያለ የቡርዧ ጠጋኝነትና እርቅ ፈላጊነትን መግለጽ ማለት ነው ። ቋሚ ቅራኔዎችን መሸሽ ፣ ሙሉ ጥልቀታቸውን ከመግለጽ ፋን ታ በጣም ጠቃሚዎቹን መዘንጋት ፤ ይህ ነው ከማርክሲ ዝም ጋራ ምንም ዝምድና የሌለው የኮትስኪ ንድፈ ሃሣብ። የዚህ ዓይነቱ « ንድፈ — ሃሣብ » ከኩኖው ንድፈ ሀሣብ ጋር ያለውን አንድነት ለማንጸባረቅ ብቻ ይረዳል ።

« ፍጹም ምጣኔ — ሀብታዊ ከሆነ አመለከካት » ይላል ኮትስኪ ሲጽፍ « ካፒታሊዝም በአንድ አዲስ የዕ

ድገት ደረጃ - ውስጥ ፣ የልዕለ ኢምፔሪያሊዝም የዕድገት ደረጃ ፣ የካርቴሎችን የውጪ ፖሊሲ አድርጎ ማስፋፋት የዕድገት ደረጃ ውስጥ መንዝ ይኖርበታል[90] ። ይህም ማለት ልዕለ ኢምፔሪያሊዝም በመካከል ትግል የሌለበት የዓለም ኢምፔሪያሊዝሞች ውህደት ፣ በካፒታሊዝም ውስጥ ጦር ነቶች የሚቆሙበት የዕድገት ደረጃ ፣ «በዓለም አቀፍ ደረጃ የተዋሃደው ገንዘባዊ ወረት በጋራ ዓለምን የመበዝበዝ[91] የዕድገት ደረጃ ማለት ነው ። »

ይህ «ልዕለ ኢምፔሪያሊዝም» ምንያህል ሙሉ በሙሉ ከማርክሲዝም ተገንጥሎ እንደሚሄድ ለማሣየት በኋላ እንመለስበታለን ። ለጊዜው ከዚህ ጽሑፍ አጠቃላይ ዕቅድ ሣንወጣ ፣ ትክክለኛውን የምጣኔ ሀብት መረጃ መመ ርመር ይኖርብናል ። « ከፍጹም ምጣኔ—ሀብታዊ አመ ለካከት » « ልዕለ ኢምፔሪያሊዝም » ሊከሰት ይችላል ወይንስ ልዕለ ትርጉም የለሽ ሃሣብ ?

ፍጹም ምጣኔ ሀብታዊ አመለካከት የሚለው ሃሣብ « ፍጹም » ማደብዘዝ ከሆነ ፣ ሊባል የሚችለው ሁሉ በሚከተለው ሃሣብ ሊጠቃለል ይችላል ። ዕድገት ወደ ሞኖፖሊዎች ያዘግማል ፤ ስለሆነም ወደ ዓለም አቀፍ ነጠላ ሞኖፖሊ ወደ ዓለም አቀፍ ነጠላ ትረስት ይህ የማ ይካድ ሀቅ ነው ፤ ሆኖም « ዕድገት » የምግብ ዓይነትን በቤተ—ሙከራ ወደ ማምረት « ይጓዛል » ብሎ የማለትን ያህል ትርጉም የለሽ ነው ። በዚህም መንፈስ የልዕለ ኢምፔሪያሊዝም « ንድፈ ሃሣብ » «የልዕለ ግብርና ንድፈ ሃሣብ » ሊኖረው ከሚችለው ያላነሰ ትርጉም የለሽ ሃሣብ ይሆናል ።

ይሁንና በሃያኛው ክፍለ ዘመን ላይ የተጀመረውን ታሪካዊ ተጨባጭነት ያለውን ከፍተኛ ወቅት እንደገንዘ

ባዊ ወረት ታሪካዊ ወቅት «ፍጹም ምጣኔ ሀብታዊ ሁኔ ታዎች ከሆነ የምንነጋገረው ሙት ለሆነው « ልዕለ ኢም ፔሪያሊዝም » (በተለይ ጸረ ተራማጅ የሆነ ዓላማን የሚ ያገለግል ፡ ማለትም ተጨባጭ ተጻራሪ ቅራኔዎችን ጠለቅ ብለን ከመመልከት የሚያግድ) ሊሰጠው የሚችለው መል ስ ፣ በጊዜው ካለው የዓለም ምጣኔ ሀብት ምጣኔ ሀብታዊ እውነታዎች ጋር እንዲያነጻጽራቸው መጋበዝ ነው ። የኮ ትስኪ ፍጹም ትርጉም የለሽ የሆነው ስለ ልዕለ — ኢም ፔሪያሊዝም ፤ የሚያወራው ወሬ ከሁሉም በላይ ፣ ለኢምፔሪያሊዝም ተናሳህያን (አጕብዳጆች) ወፍጮ እህል ማቅረብ ብቻ የሆነውን ጥልቀት ያለው የተሣሣተ አስ ተሳሰብ ፡ ማለትም የገንዘባዊ ወረት ዘመን በዓለም ጣኔም ሀብት ውስጥ የማይቀረውን አለመስተካከልና ቅራኔዎች ይቀንሳል የሚለውን ሃሣብ ያራምዳል ። እንደእውነቱ ከሆነ ግን የገንዘባዊ ወረት ዘመን አለመ ስተካከልንና ቅራኔዎችን ያባብሳል ።

አር ካልዊር «ለዓለም ምጣኔ ሀብት መግቢያ»[92] በም ትለው ትንሽ መጽሐፉ ውስጥ በሃያኛው ክፍለ ዘመን መግ ቢያ ላይ ስላለው የዓለም ምጣኔ ሀብት የውስጥ ግንኙነ ቶች ተጨባጭ ሥእል ለመስጠት የሚችሉትን ፍጹምምጣኔ ሀብታዊ የሆኑትን ዋና ዋና መረጃ ለማጠቃለል ሙከራ አድርጓል ። ዓለምን በአምስት « ዋና ዋና ምጣኔ ሀብታዊ አካባቢዎች » እንደሚከተለው ከፍሎ ያቀርባል ።

1. ማዕከላዊ አውሮፓ( ከሩሲያና ከታላቋ ብሪታ ታንያ በስተቀር መላው አውሮፓ)
2. ታላቋ ብሪታንያ
3. ሩሲያ
4. ምሥራቃዊ እስያ
5. አሜሪካ

ቅኝ ግዛቶችን ከቅኝ ገዢዎቻቸው ጋር አጣምሮ ነው ያቀረባቸው ። « እንደአካባቢው » ያልተካፋፈሉትን እንደ ፐርሺያ ፥ (አሁን ኢራን) አፍጋሀኒስታንና አረቢያ ያሉትን ከእስያ ፥ ሞሮኮንና አቢሲንያን (አሁን ኢትዮጵያ) ከአፍሪካ ፤ ወ. ዘ. ተ. « ትቷቸዋል » ።

ስለነዚህ አካባቢዎች የሚጠቀሰው የምጣኔ ሀብት መረጃ አጭር ማጠቃለያ የሚከተለው ነው ።

| ዋና ዋና የምጣኔ ሀብታዊ አካባቢዎች | የአካባቢ ስፋት | ሕዝብ | መጓጓዣ | | ንግድ | የኢንዱስትሪ ውጤት | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | ሚሊዮን ካሬ ኪሎ ሜትር | በሚሊዮን | የባቡር መስመር ሺህ ኪሎ ሜትር | የንግድ መርከብ ሚሊዮን ቶንስ | ማስመጣትና መላክ በሺህ ሚሊዮን ማርክስ | የከሰል /በሚሊዮን ቶንስ/ | የብረት በሚሊዮን ቶንስ | የጥጥ ማጠንጠኛዎች ● በሚሊዮን |
| 1. ማዕከላዊ አውሮፓ | 27.6 /23.6/ | 388 /146/ | 204 | 8 | 41 | 251 | 15 | 26 |
| 2. እንግሊዝ | 28.9 /28.6/ | 398 /355/ | 140 | 11 | 25 | 249 | 9 | 51 |
| 3. ሩሲያ | 22. | 131 | 63 | 1 | 3 | 16 | 3 | 7 |
| 4. ምሥራቃዊ እስያ | 12 | 389 | 8 | 1 | 2 | 8 | 0.02 | 2 |
| 5. አሜሪካ | 30 | 148 | 379 | 6 | 14 | 245 | 14 | 19 |

በካፒታሊዝም በከፍተኛ ደረጃ የዳበሩ (በመጓጓዣ ፥ በንግድና በኢንዱስትሪ በከፍተኛ ደረጃ ያደጉ) ሶስት አካባቢዎች እናያለን ፥ የማዕከላዊ አውሮፓ ፥ የእንግሊዝና የአሜሪካን አካባቢዎችን ። ከነዚህ ውስጥ ሶስቱ ዓለምን በቁጥጥራቸው ሥር ያዋሉ ናቸው ። እነሱም ጀር

መን ፣ ታላቋ ብሪታንያና የተባበሩት አሜሪካ ናቸው ። በነ ዚህ አገሮች መካከል ያለው ትግልና የኢምፔሪያሊስት ፉክክር ፣ ጀርመን በጣም አነስተኛ ስፋት ስላላትና ቅኝ ግዛቶችዋም ጥቂት በመሆናቸው የከረረ ሆኗል ፤ በተጨ ማሪም የማዕከላዊ አውሮፓ መፈጠር የወደፊት ጉዳይ ሆኗል፤ይህም በሞትና ሽረት ትግል ጊዜ ነው የተፈጠረው ። ለጊዜው የመላው አውሮፓ መለያ ባሕርይ የፖለቲካ ኅብ ረት ማጣት ነው ። በእንግሊዝና በአሜሪካ አካባቢዎች በሌላ በኩል የፖለቲካ መጠናከር ከፍተኛ ዕድገት አግኝ ቷል ። ይሁን እንጂ የአንደኛው ቅኝ ግዛት ቁጥር መብዛ ትና የሌላው ማነስ ሰፋ ያለ አለመመጣጠን አስከትሏል ። ያም ሆኖ በቅኝ ግዛቶች ውስጥ ካፒታሊዝም ገና ዕድገት መጀመሩ ነበር ። ደቡብ አሜሪካንም ለመያዝ የሚደረ ገው ትግል ይበልጥ እየተጧጧፈ ነው ።

ካፒታሊዝም ትንሽ ዕድገት ያሳየባቸው ሁለት አካ ባቢዎች አሉ ። እነሱም ሩሲያና ምሥራቃዊ እስያ ናቸው። በሩሲያ የሕዝቡ ብዛት ትንሽ ሲሆን በእስያ በጣም ብዙ ነው ። በሩሲያ የፖለቲካው መጠናከር ከፍተኛ ሲሆን በእስያ በፍጹም የለም ። የቻይና መከፋፈል ገና መጀመሩ ሲሆን ለመከፋፈልም በተባበሩት አሜሪካ ፣ በጃፓን ፤ ወ.ዘ. ተ. መካከል ያለው ትግል እየተፋፋመ ነው ።

እንግዲህ ይህንን ሀቅ ፣ ሠፊ የምጣኔ-ሀብትና የፖለ ቲካ ሁኔታዎች ፣ የተለያዩ ሀገሮች በጣም የተዛባ የዕድ ገት ደረጃ ያላቸው መሆኑን ፣ ወ. ዘ. ተ ፤ እና በኢምፔሪያ ሊስት መንግሥታት መካከል ያለውን አመጻዊ ትግል ፣ ከኮትስኪ ኢምንት « ሠላማዊ » ልዕለ ኢምፔሪያሊዝም

« አፈታሪክ ጋር እናወዳድር ። ይህ የደነገጠ ፈሪሣዊ ከሀቅ ለመራቅ የሚያደርገው የጸረ ተራማጅ ሙከራ አይደለ ምን ? እነዚህ ኮትስኪ በሃሣብ ቀርጾ የሚያስቀምጣቸው ካርቴሎች ፣ « የልዕለ ኢምፔሪያሊዝም » ጽንሶች (ልክ « አንድ ሰው ከኒኖችን በላቦራቷር መመረት የልዕለ ግብ ርና ፅንስ ሊል እንደሚችል ሁሉ ማለት ነው ) የዓለም መከፋፈልና መልሶም መከፋፈሉ የሠላማዊ መከፋፈል ሰላማዊ ወዳልሆነ መከፋፈል በተገላቢጦሽም ጭምር እንደምሣሌ ሊወሰድ አይችልምን ? ጀርመንም የተካፈለ ችበት መላ ዓለምን በሠላማዊ መንገድ የከፋፈለው ፣ ለም ሣሌ ዓለም አቀፋዊው የምድር ባቡር ስንዲኬት ፣ ወይ ንም ዓለም አቀፋዊው የንግድ መርከብ ትረስት ፣ የአሜሪ ካና ሌላም ገንዘባዊ ወረት በአሁኑ ወቅት ሰላማዊ ባልሆነ በማንኛውም ዘዴ እየተለወጠ በሚሄደው የኃይሎች አዲስ ግንኙነት መሠረት ዓለምን መላልሶ በመከፋፈሉ ላይ አይደለምን የዋለው ?

ገንዘባዊ ወረትና ትረስቶች የዓለምን ምጣኔ — ሀብት የተለያዩ ክፍሎች የዕድገት ፍጥነት ልዩነት በመ ቀነስ ፈንታ ያባብሱታል ። አንድ ጊዜ የኃይሎች ግንኙ ነት ከተለወጠ በኋላ ፣ በካፒታሊዝም ውስጥ ከኃይል በስ ተቀር ምን ዓይነት የቅራኔዎች ሌላ መፍትሔ ሊኖር ይች ላል ? በዓለም ምጣኔ — ሀብት ውስጥ በካፒታሊዝምና በገንዘባዊ ወረት የተለያዩ የዕድገት ደረጃዎች ላይ የባቡር[94] መስመር ስታትስቲክስ ዓይነተኛ የሆነ ትክክለኛ መረጃ ያቀርባል ። ባለፉት አሥር ዓመታት የኢምፔሪያሊዝም ዕድገት ውስጥ የባቡር መስመሮች ጠቅላላ ርዝመት እንደ ሚከተለው ተለውጧል ፡—

የባቡር መስመሮች
(በሺ ኪ. ሜትሮች)

| | 1890 | | 1913 | | ጭማሪ + | |
|---|---|---|---|---|---|---|
| አውሮጳ . . . . . . . | 224 | | 346 | | | +122 |
| ዩናይትድ ስቴትስ . . | 268 | | 411 | | | +143 |
| ቅኞች በሙሉ . . . | 82 | | 210 | | +128 | |
| የእስያና የአሜሪካ ነጻና | | 125 | | 347 | | 222 |
| ከፊል ነጻ መንግሥት | 43 | | 137 | | 94 | |
| ጠቅላላ | 617 | | 1,104 | | | |

ስለሆነም የባቡር መስመሮች ዕድገት በአሜሪካና በእሲያ በሚገኙ ቅኞችና ነጻ መንግሥታት ውስጥ (እና ከፊል ነጻ) እጅግ የተፋጠነ ነበር ። እዚህ ፣ እንደምናውቀው ፣ የአራት ወይም የአምስት ታላላቅ ካፒታሊስት መንግሥታት ገንዘባዊ ወረት አጠያያቂ አቅጣጫ ይይዛል። በእስያና በአሜሪካ ባሉ ቅኞችና ሌሎች አገሮች ውስጥ ሁለት መቶ ሺ ኪ. ሜ. አዲስ የባቡር መስመሮች በተለይ ጥሩ ምላሽ በሚአስገኙ ልዩ ዋስትናዎችና ለዐረብ ብረት ሥራዎች ትርፋማ ትዕዛዞች ፣ ወዘተ . . . ከ40,000 ሚሊዮን ማርኮች በላይ የዋለ አዲስ ወረትን ይወክላል ።

ካፒታሊዝም በከፍተኛ ፍጥነት የሚአድገው በቅኞችና ከባሕር ማዶ ባሉ አገሮች ውስጥ ነው ። ከባሕር ማዶ ካሉ አገሮች መካከል አዲስ ኢምፔሪያሊስት ኃይላት እየታዩ ናቸው (ለምሳሌ — ጃፓን) ። በዓለም ኢምፔሪያሊዝሞች መካከል ያለው ትግል ይበልጥ ትብ እየሆነ እየሄደ ነው ። እጅግ ትርፋማ በሆኑት ቅኞዊና የባሕር ማዶ አገሮች ድርጅቶች ላይ በገንዘባዊ ወረት የተጣለባቸው ተጨማሪ ግብር እየጨመረ ነው ። በዚህ « የምርኮ » ወይም « የዝርፊያ » ክፍፍል ላይ ፣ ከመጠን በላይ ብዙው ክፍል የሚሄደው ሁልጊዜም በምርት ኃይሎቻ

ቸው ፈጣን ዕድገት ከፍተኛውን ቦታ ለሚይዙት አገሮች ነው ። ታላላቅ አገሮችንና ቅኞቻቸውን በሚመለከት ረገድ፤የባቡር መስመሮች ጠቅላላ ርዝመት እንደሚከተ ለው ነበር ።

| | 1890 | 1913 | |
|---|---|---|---|
| | (በሺ. ኪ. ሜ.) | | |
| የዩናይትድ ስቴትስ | 268 | 413 | +145 |
| የእንግሊዝ ግዛት . . | 107 | 208 | +101 |
| ሩሲያ . . . . . . | 32 | 78 | + 46 |
| ጀርመን . . . . | 43 | 68 | + 25 |
| ፈረንሳይ . . . . | 41 | 63 | + 22 |
| የአምስቱ ኃያላን ጠቅላላ | 491 | 830 | +339 |

ስለዚህ ጠቅላላ በሕልውና ላይ ካሉት የባቡር መስ መሮች 80 በመቶው በአምስቱ ታላላቅ ኃያላን መንግሥ ሥታት እጅ ውስጥ ደልበዋል።ሆኖም በእነዚህ መስመር መሮች ባለቤትነት መድለብ ፥ የገንዘባዊ ወረት መድለብ ከፈረንሳውያንና እንግሊዝ ሚሊየነሮች ጀምሮ ይህ ነው የማይባል ታላቅነት አለው ፤ ለምሳሌ ፥—በአሜሪካ፥ ሩሲ ያና ሌሎች የባቡር መስመሮች ውስጥ የከፍተኛ መጠን ድርሻና ቦንዶችን (ሠነዶችን) ያዝዛሉ ።

ለቅኞቿ ምሥጋና ይግባቸውና ፥ ታላቋ ብሪታኒያ የባ ቡር መስመሮ «ቿን» እርዝመት የጀርመንን አራት እጥፍ ያህል በ100,000 ኪ. ሜ. አሳድጋለች ። እንዲህም ሆና በጀርመን የምርት ኃይሎች ዕድገት ፥ በተለይም የከሰልና የብረት ኢንዱስትሪዎች ዕድገት — ፈረንሳይንና ሩሲያን ሳንጠቅስ — በዚህ ዘመን ፥ ከእንግሊዝ ፥ በበለጠ ተወ ዳዳሪ የሌለው ፍጥነት እንደነበረው የታወቀ ነበር ። በ1892 ጀርመን 4,900,000 ቶን የፒግ ብረትና እንግሊዝ ደግሞ 6,800,00 ቶን አምርተዋል ፤ በ1912 ጀርመን 17,600,000

ቶን ፣ እንግሊዝ 9,000,000 ቶን አምርተዋል ። ስለዚህ ጀርመን በዚህ መልክ በእንግሊዝ ላይ ሠፊ የበላይነት ቦታ ነበራት[95] ። ጥያቄው፣ በካፒታሊዝም ውስጥ በምርት ኃይሎች ዕድገትና በሌላበኩል በወረት መድለብና በቅኝ ችና በገንዘባዊ ወረት የተፅዕኖ ክልል ክፍያ መካከል ያለ ውን አለመመጣጠን ለመወጣት ፣ ከጦርነት በቀር ሌላ ምን ዘዴ አለ ? የሚለው ነው ።

## ምዕራፍ ስምንት

# የካፒታሊዝም ጥባቴነትና (ፓራሲቲዝም) መበስበስ ፤

እንግዲህ ብዙዎች ውይይቶች በቂ ግምት ያልሰጡ ትን ሌላውን የኢምፔሪያዝምን ጉልህ ገጽታ (አስፔክት) እንመርምር ፣ ማርክሲስት ካልሆነው ሆብስን ጋር ሲወዳደር ማርክሲስቱ ሂልፈርዲንግ ካሉት ጉደለቶቹ መካከል በዚህ ነጥብ ላይ አንድ እርምጃ ወደ ኋላ ተራ ምዷል ። የኢምፔሪያሊዝምን ዓይነተኛ ጠባይ የሆነው ጥባቴነትን አመለክታለሁ ። እንደተረዳነው ጥልቅ የሆ ነው የኢምፔሪያሊዝም የምጣኔ ሀብት መሠረት ሞኖፖሊ ነው ። ይህም ፣ በካፒታሊዝም ያደገውና በካፒታሊ ዝም ፣ በሸቀጥ ምርትና በውድድር አጠቃላይ አካባቢ የሚኖረው ፣ ከዚህም አጠቃላይ አካባቢ ጋር ቋሚና መፍ ትሔ የሌለው ቅራኔ የሚፈጥረው ካፒታሊስት ሞኖፖሊ ነው።ይሁን እንጂ፤እንደማንኛውም ሞኖፖሊ፣የመበስበስና የመከርፋት አዝማሚያ ያስከትላል ። ለጊዜውም ቢሆን የሞኖፖሊ የዋጋ ተመኖች (ፕራይስስ) የተወሰኑ ስለሆነ

የቴክኒካል ብሎም ሌሎች እርምጃዎች አንቃናቂው ምክ ንያት ለተወሰነ ጊዜ ከመጥፋቱም በላይ ሆን ተብሎ ቴክኒካዊ እርምጃውን ወደ ኋላ ከመገፋቱ የምጣኔ ሀብት ሁኔታዎች ይፈጠራሉ ። ለምሣሌም በአሜሪካ አንድ አው ንስ የሚባል ሰው የጠርሙሶችን መፈብረክ የለወጠ አንድ መሣሪያ ፈልስፎ ነበር ። የጀርመን የጠርሙስ ማምረቻ ካርቴል የኦውንስን የመሥራትና የመሸጥ መብት (ፓቴ ንት) ገዝቶ ነበር ። ይሁን እንጂ አፍኖ በመያዝ ሣይጠቀ ምበት ቀርቷል ። በእርግጥ ፥ በካፒታሊዝም ውስጥ ያለ ሞኖፖሊ በዓለም ገበያ ያለውን ውድድር ለብዙ ጊዜ ሙሉ በሙሉ ሊያስቀረው አይችልም።(ይህም፥ልዕለ ኢምፔ ሪያሊዝምን ትርጉም የለሽ ከሚያደርጉት ምክንያቶች አንዱ ነው) ቴክኒካዊ መሻሻሎችን በማስተዋወቅ የማ ምረቻ ወጪን የመቀነስና ትርፍን የመጨመር ዕድል የለ ውጥን አቅጣጫ እንደሚይዝ ጥርጥር የለውም ። ይሁን እንጂ የሞኖፖሊ ጠባይ የሆነው የመከርፋቱና የመበስ በሱ አዝማሚያ ፥ በአንዳንድ ኢንዱስትሪ ቅርንጫፎች በአንዳንድ አገሮች ፥ ለተወሰነ ጊዜ ቅድሚያን በመያዝ መሥራቱን ይቀጥላል ። ሠፋፊ ፥ ሃብታም ወይንም መል ካም አቀማመጥ ያላቸው ቅኝ ግዛቶች በሞኖፖሊ ሲያዙ በተመሣሣይ አቅጣጫ ይንቀሳቀሳሉ ።

በተጨማሪም ፥ ኢምፔሪያሊዝም እንዳየነው ከ100, 000, እስከ 150,000 ሚሊዮን ፍራንክ የሆነ አያሌ የገን ዘብ ወረት ለዋስትና በጥቂት አገሮች ማከማቸት ነው ። ስለዚህም ነው የአንድ መደብ ወይንም ደግሞ ማለትም ኑሮአቸውን ኩፖኖችን በመቁረጥ አራጣ አበዳሪዎች የሚ መሩ የሕብረተሰብ አባላት ደረጃ ፥ በማናቸውም የምርት ድርጅት የማይሣተፉ ፥ ሙያቸው በዝና መቀመጥ የሆነ ከፍተኛ ዕድገት ያሣዩት።ከኢምፔሪያሊዝም ጠቃሚ የም

ጣኔ ሀብት መሠረቶች አንዱ የሆነው ፣ የወረት ወደ ውጭ መላክ ፣ አራጣ አበዳሪዎችን ከምርት በበለጠ በመገንጠል፥ ቅኝ ግዛቶችንና የባህር ማዶ አገሮችን ወዝ በመበዝበዝ የሚ ተዳደሩትን መላ አገሮች የጥባቴነት ማህተም ያትምባቸ ዋል ። « በ1893 » ይላል ሆብሰን ሲጽፍ « በውጭ አገር ወጭ የተደረገው የእንግሊዝ ወረት ከጠቅላላው የብሪታንያ ኃብት ውስጥ አሥራ አምስቱን እጅ በመቶ ይይዛል ።»*96 በ1915 ዓመተ ምህረት ይህ ወረት በሁለት ተኩል እጅ እንደጨመረ ለአንባቢው ለማስታወስ እወዳለሁ ። « ወራ ሪው ኢምፔሪያሊዝም » ይላል ሆብሰን ጽሁፉን በማራ ዘም « የግብር ከፋዩን ኪስ የሚያሟጥጥ ፣ ለአፈብራ ኪው ወይንም ለነጋዴው ምንም ረብ የሌለው . . . ገንዘ ቡን ለሚያውለው ሰው ትልቅ የገቢ ምንጭ ነው ። በመላ የውጭና የቅኝ ግዛት ንግዱ ፤ የምትልካቸውና የምታስ መጣቸው እቃዎች ፣ ታላቋ ብሪታንያ ከኮሚሽን የምታገ ኘው የአመት ገቢ በ2½ እጅ በመቶ የተወሠደ የ800,000, 000 ፓውንድ ስተርሊንግ የሽያጭ ግብር ተወስዶ 18,000, 000 (ወደ 170 ሚሊዮን ሩብል የሚጠጋ) ፓውንድ ስተ ርሊንግ እንደሆነ በ1899 ሰር አር ጊፈን ገምቷል ።» ይህ ገንዘብ አያሌ ቢሆንም ፣ ከ90 ሚሊዮን እስከ 100 ሚሊ ዮን ፓውንድ ስተርሊንግ በሚውለው የአራት አበዳሪዎች ገቢ የሚገለጸውን የታላቋን ብሪታንያ እውቅ አጥቂነት ማወቅ አይችልም ።

የአራጣ አበዳሪዎች ገቢ ከፍተኛ «ነጋዴ» የሆኑ አገ ሮች ከውጪ ንግድ ከሚያገኙት ገቢ በአምስት እጥፍ ይበል ጣል ።ይህ ነው የኢምፔሪያሊዝምና የኢምፔሪያሊስት ጥባቴነት ይዘት (ኤሰንስ) ።

በዚህ ምክንያት «የአራጣ አበዳሪዎች መንግሥት፣» ስለኢምፔሪያሊዝም በሚቀርበው በምጣኔ ሀብታዊ ሥነ

ጽሁፍ ውስጥ መጠቀስ የተለመደ ሆኗል ። ዓለም ፣ እፍኝ ፤ በማይሞሉ በዝባዥና በርካታ ዕዳ የተዘፈቁ መንግሥታት መካከል ተከፋፍላለች ። በውጪ መዋእለ ንዋይ ዝርዝር ላይ የከፍተኛውን ቦታ የያዙት» ይላል ሽልዝ ፥ ጋቨርኒትዝ «የፖለቲካ ጥገኞች ወይንም የተዛመዱ አገሮች ናቸው ፤ ታላቋ ብሪታንያ ለግብፅ ፣ ለጃፓን ፣ ለቻይናና ፣ ለደቡብ አሜሪካ ብድር ትሠጣለች ። የባህር ኃይሏ ፣ አስፈላጊ ሲሆን እንደ ተቆጣጣሪ ሆኖ ይሠራል ። ባለዕዳዎቹ እንዳ ያዋርዷት የታላቋ ብሪታንያ የፖለቲካ ኃይል ይከላከል ላታል ።*[97] በውጪ የወረት መዋእለ ንዋይ ብሔራዊ ምጣኔ ሀብታዊ ሥርአት፥ በሚል አርእስት ስር በጻፈው መጽሐፍ ውስጥ ሳርትሪየስ ቦን ዋልተርሃውስን ሆላንድን ለ«አራጣ አበዳሪዎቹ መንግሥት» እንደ ሞዴል ሲያቀርብ ታላቋ ብሪ ታንያና ፈረንሣይን እንደ ሆላንድ ሁሉ ተመሣሣይ አቋም እየያዙ መሆናቸውንም ጠቅሷል[98]። XX ሺልደር አምስት በኢንዱስትሪ የበለጸጉ አገሮች « በእርግጥ የታወቁ አበ ዳሪ አገሮች» ሆነዋል የሚል ሃሣብ አለው ። እነዚህም አገሮች ታላቋ ብሪታንያ ፣ ፈረንሣይ ፣ ጀርመን ፣ ቤል ጅግና ስዊዘርላንድ ናቸው ። በዝርዝሩ ውስጥ ሆላ ንድን ያልጨመረው « በኢንዱስትሪ ገና በደንብ ያልዳ በረች» በመሆኗ ነው[99] ። XXX አሜሪካ ብቻ የሌሎች የአ ሜሪካ አገሮች አበዳሪ ነች ።

« ታላቋ ብሪታንያ » ይላል ሹልዝ — ጋቨርኒትዝ « ከኢንዱስትሪያል መንግሥት ወደ አበዳሪ መንግሥት ቀስ በቀስ እየተሸጋገረች ነው ። የኢንዱስትሪ ውጤትና የተፈበረኩ እቃዎች ወደ ውጪ መላክ እየጨመረ ቢሄ ድም ፣ የወለድና የትርፍ ድርሻ (ዲቪደንድ) ፣ መተማመኛ መስጠት ፣ ከሚሽንና የመላውን የብሔራዊ ምጣኔ ሃብት በአንጻሩ ማደግ ጠቃሚ ሆኖ ተገኝቷል ። በኔ ግምት የኢ

ምፔሪያሊዝምን አሽቅቦ መውጣት የምጣኔ ሀብት መሠረት ያበጀው በትክክል ይኸው ነው ። የአንድ ዕቃ ሻጭ ከገዢው ጋር ከሚኖረው ግንኙነት ይልቅ አበዳሪው ከተበዳሪው ጋር የሚኖረው ይበልጣል[100]።XXX«ጀርመንን በሚመለከት ፣ ኤ. ላንስበርግ ፣ የበርሊን ዳይ ባንክ አታሚ በ1911 « ጀርመን የአራጣ አበዳሪ መንግሥት » በሚል ርዕስ ባወጣው ጽሑፍ የሚከተለውን ብሏል ፣ « በጀርመን ውስጥ ያሉት ሕዝቦች ፈረንሣይ የምታራምደውን አራጣ አበዳሪ የመሆን ፍላጐት ፣ ያንኳሥጡታል ። ይሁን እንጂ ከቡርዧው አንጻር ሲታይ በጀርመን ያለው ሁናቴ እያደር እንደ ፈረንሣይ እየሆነ መሔዱን ዘንግተውት ነው[101] ።» XXXXX

የአራጣ አበዳሪ መንግሥት ጥባቴያዊ (በሌላው ላይ የሚኖር) ፣ እየበሰበሰ የሚሄድ የካፒታሊዝዝም መንግሥት ነው ። ይህም ሁናቴ ጉዳዩ በሚመለከታቸው ሃገሮች ሕብረሰባዊና ፖለቲካዊ ሁኔታዎች ላይ በአጠቃላይና በሁለቱ መሠረታዊ የወዝ አደሩ ንቅናቄ መስመሮች ላይ በተለይ ፣ ተፅዕኖ ከማድረግ አይመለስም።

በተቻለ መጠን ቁልጭ ባለ መንገድ ይህን ሐቅ ለመግለጽ አስተማማኝ ምስክር ሊሆን የሚችለውን ሆብሰንን ልጥቀስ። እሱ በመጀመሪያ ደረጃ በእምነት ላይ የተመሠረተ የማርክሲስትነት ዝንባሌ ስለሌለውና ፣ በሁለተኛ ደረጃ እንግሊዛዊ በመሆኑ በቅኝ ግዛቶች ፣ በገንዘባዊ ወረትና በኢምፔሪያሊስት ልምድ ሀብታም ስለሆነቺው አገር የውስጥ ሁኔታ በሚገባ ስለሚያውቅ ለምስክርነት ብቁ ነው ። የእንግሊዝና የሆላንድ ጦርነት ገና ከሃሣቡ ሣይጠፋ በኢምፔሪያሊዝምና «በባለገንዘቦቹ» ፍላጐቶች ከኮንትራት፤ ከእቃ ማቅረብ፤ ወዘተርፈ የሚያገኙት እያደገ በሚሔደው ትርፋቸው መካከል ያለውን ግንኙነት በመግለጽ ሲጽፍ

« የዚህ በርግጥ ጥባቴያዊ ፖሊሲ ሥራ አስኪያጆች (የድ ሬክተሮች) ካፒታሊስቶች ቢሆኑም እነዚሁ ፍላጐቶች ሌሎችንም የሠራተኛ መደቦች ያንጓሉ ። በብዙ ከተ ሞች ዋና ዋና የሆኑት የንግድ ሥራዎች በመንግሥት ቅጥ ረኛነትና በኮንትራቶች ላይ ጥገኛ ናቸው ። የብረትና የመ ርከብ ሥራ ማዕከሎች ለዚህ ሐቅ እንደማስረጃነት ሊቀ ርቡ የሚችሉ ናቸው ። « በጸሐፊው አስተሳሰብ ፥ የቀድሞ ግዛተ አጼዎችን ያዳከሟቸው ሁለት ሁኔታዎች ናቸው ። እነሱም « (1) ምጣኔ ሀብታዊ ጥባቴነት » ። እና (2) ከተ ገዢው ሕዝብ መካከል የተመለመሉ ወታደሮችን ማጿ ቋም ናቸው ። « ገዢው መንግሥት ክፍለ ሃገሮችን ፥ ቅኝ ግዛቶቹንና ጥገኞችን በመጠቀም የገዢውን መደብ የማበልጸግና ዝቅተኛው መደብ ደግሞ ዝም ብሎ እን ዲገዛ አፉን ለመዝጋት ጉቦ በመስጠት የመሥራት ም ጣኔ ሀብታዊ ልምድ አለው ። » ምንም ዓይነት ቅርጽ ይኑረው፥ የዚህ አይነቱ ጉቦ ምጣኔ ሀብታዊ ችሎታ ከፍ ተኛ የሞኖፖሊስት ትርፍ እንደሚጠይቅ ለማከል እወ ዳለሁ ።

የሁለተኛውን ሁናቴ አስመልክቶ ሆብሰን ሲጽፍ « የኢምፔሪያሊዝምን ዓይነ ጭፍንነት ከሚያረጋግጡት እንግዳ ምልክቶች(ሲምፕተምስ) አንዱ ጥንቃቄ በጐደ ለው ግድ የለሽነት ታላቋ ብሪታንያ ፥ ፈረንሣይና ሌሎቹ ኢምፔሪያሊስት መንግሥታት እዚህ አደገኛ ጥገኝነት ውስጥ መዘፈቅ ነው ። በዚህ ታላቋ ብሪታንያ ቀድማ ሔዳለች ። የህንዱን ግዛት . . አጼ ያስገበርንባቸው ይበ ልጡን ውጊያዎች የተካሄዱት ያገሩን ተወላጅ በመጠ ቀም ነው ። በሕንድ ፥ ከቅርብ ጊዜ ወዲህም በግብጽ ከፍተኛ መደበኛ ሠራዊት በእንግሊዝ የበላይ ተቆጣጣሪ ነት ሥር ተመድበዋል ። በአፍሪካ ግዛቶቻችን ውስጥ ፥

ከደቡቡ ክፍል በስተቀር ፣ ይበልጡን ውጊያ የተዋጉልን የሣገሬው ተወላጆች ናቸው ።» ለቻይና መቀረማመት ወደ ፊት ሊገኝ ስለሚችለው ምጣኔ ሀብታዊ ጥቅም ግምት ሆብሰን የሚከተለውን ይላል ። «የምዕራብ አውሮፓ ይበ ልጡ ክፍል በደቡብ ኢንግላንድ ፣ በሪቤራና በቱሪስት በተጥለቀለቀው ወይንም የመኖሪያ ክፍል በሆነው ኢጣ ሊያና ሲዊዘርላንድ እንደታየው አይነት የባላገር መሬት አቋምና ጠባይ ሣይዙ አይቀሩም ። ይህም ማለት እፍኝ የማይሞሉ መሳፍንታዊ የገዢ መደብ አባሎች (አሪስ ስቶክራቶች) የትርፍ ክፍያና የጡረታ አበል ከአያሌ የነሱ ተከታዮች ከሆኑ ባለሙያዎችና ነጋዴዎች ከዚህም በላይ የግል አገልግጋዮችና በማጓጓዣ የሥራ መስክና አላቂ እቃዎችን በማምረት ላይ የሚሠማሩ ሠራተኞችን ጭምር ከሩቅ ምሥራቅ ያገኛሉ ማለት ነው ። የሣገሩ ምግብና የም ርት ውጤቶች ከእስያና ከአፍሪካ እንደ እጅ መንሻ እየጐ ረፈላቸው ዋና የደም ሥር የሆኑ ኢንዱስትሪዎችም ሁሉ ወድመው ነበር ። የምዕራባውያን መንግሥታት መተባ በር ፣ እስከአሁን የአለምን ስልጣኔ ወደፊት ከማራመዱ የተነሳ የምዕራብ ጥባቴንትን አደገኛ እልቂት ሊያስ ከትሉ የሚችሉ የምዕራብ አውሮፓ ታላላቅ ኃያላን ፌዴ ሬሽን ፣ ሊደረግ እንደሚችል በቅድሚያ አስጠንቅቀናል።

የተወሰኑ በኢንዱስትሪ የገፉ ገዢ መደባቸው እንደፈለገ የሚያደርጋቸውን ሰፊ ተከታዮቻቸውን የሚረዱበትን ገን ዘብ በእጅ መንሻ መልክ በእስያና በአፍሪካ የሚያገኙ ፣ ብሔሮች እንደ ቀድሞ የሣገር ውስጥ ኢንዱስትሪዎች በሆኑት በእርሻና በአፋብሪካነት ላይ በማተኮር ፈንታ በጥቂት ገንዘባዊ የገዢ መደብ ተቆጣጣሪነት የግል ሥራ መስራትና በጥቃቅን የኢንዱስትሪ አገልግሎት ላይ እን ዲሠማሩ እንደሚደረግም በቅድሚያ ጠቁመናል ። ይህን

ንድፊ ሃሣብ (ሰፋ ያለ የጥቅም ትልም (ፕሮስፔክት) ማለቱ ሣይሻል አይቀርም) መጤን እንደሌለበት አድርገው አል ዋጥ የሚላቸው ከላይ ወደ ተጠቀሰው ሁናቴ የተለወጡ ትን የደቡባዊ ኢንግላንድ ቀበሌዎች የምጣኔ ሀብትና የህብረተሰብ ሁናቴዎች ይመርምሩ ። ዛሬ የዚህን ሥር አት ተመሣሣይ ካፒታሊስቶች ፣ ባለገንዘቦች ፣ የመዋእለ ወረት ባለቤቶች (ኢንቬስተርስ)ና የፖለቲካና የታላላቅ ንግድ ድርጅቶች ባለሥልጣኖች፣ ቻይናን በኤኮኖሚ ቁጥጥ ራቸው ሥር በማድረግ በዓለም እስከዛሬ ያልታወቀውን ከፍተኛ የትርፍ ክምችት (ሬዘርቫየር) በማሟጠጥና በአ ውሮፓ ውስጥ አገልግሎት ላይ በማዋል ሊመጣ በሚች ለው የከፍተኛ ደረጃ መስፋፋት ላይ ሃሣባቸውን ጣል ያደ ረጉ የዚህን ወይንም የማናቸውንም የወደፊት ሁናቴ አመ ለካከት ምናልባታዊነት ለማቅረብ ፣ ሁናቴው በጣም የተ ወሣሰበ የዓለም ኃይሎች የሚጫወቱት ቅኝትና በጣም ለቁ ጥጥር የማያመች ነው ። ይሁን እንጂ ዛሬ የምዕራብ አው ሮፓ ኢምፔሪያሊዝምን የሚቆጣጠሩት ተፅዕኖዎች ወደ ዚህ አቅጣጫ እያመሩ ናቸው ፣ የሚቋቋማቸው ካላገኙ ወይንም አቅጣጫቸውን እንዲቀይሩ ካልተደረገም ወደ ተመሣሣይ ፍጻሜ (ኮንሱሜሽን) ያመራሉ[102] ።

ደራሲው ትክክል ብሏል ። የኢምፔሪያሊዝም ኃይ ላት የሚቋቋማቸው ባይኖር ኖሮ በትክክል እሱ ወደ ገለ ጠው ያመሩ ነበር ። « የተባበሩት የአውሮፓ መንግሥ ታት » የሚለው ሃሣብም ጠቃሚነት በአሁኑ የኢምፔሪ ያሊሲት ሁናቴ ትክክለኛውን ዋጋ ነው ያገኘው ። ሆኖም በሠራተኛው መደብ ንቅናቄ በአብዛኛው አገር ጊዜያዊ ድልን የተቀዳጁ አድርባዮች እቅድ ባለው መንገድና ሣያ ወላውሉ በዚሁ አቅጣጫ « እየሠሩ» መሆናቸውንም ደራ ሲው ጨምሮ ማቅረብ ነበረበት ። ኢምፔሪያሊዝም ፣ ማለ

ትም የዓለም መከፋፈልና ከቻይና በስተቀር ሌሎችን አገ ሮች መበዝበዝ ፣ ከፍተኛ የሞኖፖሊ ትርፍ እፍኝ ለማይ ሞሉ በጣም ሀብታም አገሮች ማስገኘት ፣ የወዛደሩን የላ ይኛውን ክፍል (ስትራታ) ጉቦ በመክፈል ብሎም ለአድር ባይነት ቅርጽና ኃይል በመስጠት፣የሱን ፍላጐት በማሟላት ምጣኔ ሀብታዊ ሁኔታን ይፈጥራል ። ያም ሆኖ ኢምፔሪያ ሊዝምናበአጠቃላይ አድርባይነትን በተለይ የሚቋቋሙትን፣ ሲሺያል ለዘብተኛው (ሶሺያል ሊብራል) ሆብሰን ሊያ ያቸው የማይችላቸውን ፣ ኃይሎች ሣናስተውል ማለፍ የለብንም ። የጀርመኑ አድርባይ ጀርሃርድ ሂልደብራንድ ፣ አንድ ጊዜ ለኢምፔሪያሊዝም የቆመ በመሆኑ ከፓርቲው ተባርሮ የነበረው ፣ ዛሬ ደግሞ « ሶሺያል ዲሞክራቲክ » እየተባለ ለሚጠራው ፓርቲ መሪ ሊሆን የሚችል ፣ የቻ ይናንና የጃፓንን (ሲኖ ፣ ጃፓኒዝኮአሊሽን)[103] ጥምር ፤ ወዘተ ኃይል ለመቋቋም የሚችል «የተጠናከረ ጦር ሠራዊትና የባህር ኃይል» እንዲኖር በ «ታላቁ የእስ ልምና ንቅናቄ» ላይ በአፍሪካ ጥቁሮች ላይ «የተባበረ» እርምጃ ለመውሰድ (ከሩሲያ በስተቀር) «የተባበሩት የምዕራብ አውሮፓ መንግሥታት» የሚለውን ሆብስን የሚያስተጋ ባውን ዓላማ በሚገባ ያጠናክራል ።

በሹልዝ—ጋቨርኒትዝ መጽሐፍ ውስጥ የተሠጠው «የእንግሊዝ ኢምፔሪያሊዝም» አገላለጽ ተመሣሣዩን ጥባ ቴያዊ ባህርይ ያጋልጣል።የታላቋ ብሪታንያ ብሔራዊ ገቢ ከ1865 ዓ. ም. እስከ 1898 ዓ.ም. ባለው ጊዜ ውስጥ በእ ጥፍ ሲጨምር በዚሁ ጊዜ ውስጥ «ከውጪ» ያገኘችው ገቢ በዘጠኝ እጥፍ አድጓል ። ኢምፔሪያሊዝም « ጥሩ ነት » ጥቁሮችን በኢንደስትሪ ልምድ ማሠልጠን ሆኖ ሣለ (ያለማስገደድ ማካሔድ አይቻልምና)፣«አደገኛነቱ» ደግሞ «አውሮፓ ፣ የካባድን ሥራ ጭነትና በመጀመሪያ

የግብርናና የማዕድን ቁፋሮ ከዚያ የኢንዱስትሪ ከባድ ሥራ —በጥቁሮቹ ላይ መጫን ደሆንና እሱ ራሱ ደግሞ የአራጣ አበዳሪ ሚና በመጫወት ይረካል ። ቦዚህ አኳኋን ምናልባት ጥቁሮቹን የምጣኔ ሀብትና ብሎም የፖለቲካ ነጻነት የሚያቀዳጅበትን መንገድ ይቀይሣል ።»

በእንግሊዝ አገር ይበልጡ መሬት ከእርሻ ግልጋሎት እየተላቀቀ ለስፖርትና ለሃብታሞች የተለያየ አገልግሎት እንዲሠጥ እየተደረገ ነው ። ስኮትላንድ — ለአደንና ለሌሎች የስፖርት ተግባሮች መሳፍንት የሚውሉባት ስፍራን በሚመመለከት ረገድ « በሚስተር ካርኔጂና (አሜሪካዊው ባለ ብዙ ሚሊዮን ብር) በቀድሞ ዝናዋ » እንደምትተዳደር ይነገርላታል ። ለፈረስ ግልቢያና ለቀበሮ አደን ብቻ ኢንግላንድ በየዓመቱ 14,000,000 ፓውንድ ስተርሊንግ ታወጣለች ። በእንግሊዝ የአከራዮች (አበዳሪዎች) ቁጥር ወደ አንድ ሚሊዮን ይደርሣል ። በምርት ላይ የተሠማራው ሕዝብ ፣ ቁጥር ከጠቅላላው ሕዝብ ጋር ሲነጻጸር እያሽቆለቆለ ሄዷል ።

| | የእንግሊዝ ዌልስ የሕዝብ ብዛት /000,000/ | በመሠረታዊ ኢንዱስትሪዎች ውስጥ ሠራተኞች /000.000/ | የጠቅላላው ሕዝብ ፐርሰንት (በመቶ) |
|---|---|---|---|
| 1851 ............ | 17.9 | 4.1 | 23 |
| 1901 ............ | 32.5 | 4.9 | 15 |

የእንግሊዝን ሰርቶ አደር « የሃያኛው ክፍለ ዘመን መጀመሪያ የእንግሊዝ ኢምፔሪያሊዝም » የቡርዧው ተማሪ የሠርቶ አደሩን «የላይኛውን ክፍል» (ስትራተም) « ዝቅተኛ መደበኛውን ወዝ አደር ክፍል » በሥነ ሥርአት ለይቶ ለማስቀመጥ ግዴታ አለበት ። የላይኛው ክፍል ከጋራ ማህበራት ፣ (ኮ—ኦፕሬቲቭስ) ከሠራተኛው ማህ

በር ፡ ከስፖርት ክበቦችና ከአያሌ የሀይማኖት ዘርፎች (ሴክትስ) የተውጣጡ አባላትን ይይዛል ። «ዝቅተኛ የመ ደበኛው ወዝ አደር ክፍል» ከምንም አይነት ምርጫ የተወገደ ሲሆን የላይኛው የሠርቶ አደር ክፍል ግን በም ርጫ ስርአት ውስጥ እንዲካፈል ይደረጋል ! የእንግሊዝ ሠርቶ አደር ሁኔታ ደማቅ ቀለም ቀብቶ ለማቅረብ ሲፈ ለግ ስለ ጥቂቱ የላይኛው ወዛደር ክፍል ሁኔታ ነበር የሚወራው ። ለምሳሌ « በሎንደን ጐልቶ የሚታየው በተ ለይም የዝቅተኛው የወዝ አደር ክፍል ችግር የነበረው[104] ሥራ አጥነት በፓለቲከኞቹ በኩል ምንም ግምት አይሠ ጠውም ።*» የቡርዧ ፖለቲከኞቹና «የሶሺያሊስት» አድ ርባዮች ጉዳዩ ብለው የማያዩት ነው ማለት ነበረበት ።

ከማብራራቸው ሀቆች ጋር ዝምድና ካላቸው የኢምፔ ሪያሊዝም የተለዩ ባህርያት አንዱ ዝቅተኛ ምንዳን ከሚከፈ ልባቸውና በጣም በሥልጣኔ ኋላ ቀር ከሆኑት ሃገሮች ወደ ኢምፔሪያሊስቶቹ ሃገሮች የሚሔዱት የስደተኞች ቁጥር እየጨመረ ሲሄድ ከኢምፔሪያሊስቶቹ ሃገሮች ኋላ ቀር ወደሆኑት ሃገሮች የሚሔዱት የስደተኞች ቁጥር እየቀነሰ መሔዱ ነው ። ሆብሰን እንደተመለከተው ከ1884 ዓ.ም. ጀምሮ ከታላቋ ብሪታንያ ወደ ውጭ የሚሔዱት ስደተ ተኞች ቁጥር እየቀነሰ ሔዷል ። በዚህ ዓመተ ምህረት የስደተኞች ቁጥር 242,000 ሲሆን በ1900 ደግሞ ቁጥሩ 169,000 ነበር ። በጀርመን በ1881 ዓ.ም.ና በ1890 ዓ.ም መካከል የስደተኞቹ ቁጥር ከፍተኛ ደረጃ በመድረስ 1,453 000 ደርሶ ነበር ። በሚቀጥሉት ሁለት የአሥር አመታት (ዲኬድስ) ጊዜ ውስጥ ይህ ቁጥር ወደ 544,000 እና 341, 000 ወርዶ ነበር ። በአንጻሩ ደግሞ ከአውስትሪያ ፡ ከኢጣ ሊያን ፡ ከሩሲያና ሌሎችም ሃገሮች ወደ ጀርመን የሚገ ቡት ስደተኞች ቁጥር ጨምሮ ነበር ። በ1907 ዓ. ም. ተደ ርጐ በነበረው የሕዝብ ቆጠራ በጀርመን ውስጥ 1,342,

294 የውጪ ዜጐች እንደ ነበሩ ሲታወቅ ከነዚህም ውስጥ 440,800 የኢንዱስትሪ ሠራተኞች ፥ 257,329 ደግሞ በእ ርሻ ሥራ ላይ ተሠማርተው የነበሩ ናቸው ።*[105] በፈረንሣይ በማዕድን ሥራ ላይ ተሰማርተው ከነበሩት ሠራተኞች « ይበልጡ » የውጪ ዜጐች ሲሆኑ እነሱም የፖላንድ ፥ የኢጣሊያና የስፓኝ ሰዎች ናቸው ። ***[106] በአሜሪካ ከም ሥራቅና ከደቡብ አውሮፓ የመጡት ስደቶች በዝቅተኛ ደሞዝ የሚበዘበዙ ሲሆን የሃገሬው ተወላጆች ግን በካቦነት የሚሠሩና ደህና ደሞዝ የሚከፈላቸው ነበሩ*።[107]

ኢምፔሪያሊዝም ከሰፊው ወዛደር መካከል እየገነ ጠለ መብታቸው የተጠበቁ የጥቂት ምርጦች ክፍል የመፍጠር አዝማሚያ አለው ።

በታላቋ ብሪታንያ ኢምፔሪያሊዝም ሠራተኛውን የመከፋፈል ፥ በመካከላቸው አድርባይነትን የማጠናከርና ብሎም ንቅናቄያቸውን ለጊዜው የማዳከም አዝማሚያ የተከሠተው ከአሥራ ዘጠነኛው ክፍለ ዘመን መጨረሻና ከሃያኛው ክፍለ ዘመን መግቢያ ቀደም ብሎ እንደነበር መታወስ አለበት ። ምክንያቱም በዚህ አገር ሁለቱ የኢም ፔሪያሊዝም መለያ ባህርዮች ማለትም ፥ ሠፊ የቅኝ ግዛት መያዝና በአለም ገበያ የሞኖፖሊስትነት አቋም ፥ በአሥራ ዘጠነኛው ምዕተ - ዓመት መካከል ላይ መታየት ጀም ረው ነበር ። ማርክስና ኤንግልስ በሠራተኛው ንቅ ናቄ ውስጥ ባለው አድርባይነትና በእንግሊዝ ካፒታ ሊዝም የኢምፔሪያሊስት ባህርይ መካከል ያለውን ግን ኙነት ለብዙ ዓመታት በሥርአት ተከታትለዋል ። ጥቅ ምት 7 ቀን 1958 ዓ. ም. ለምሣሌ ኤንግልስ ለማርክስ ሲጽፍ» የእንግሊዝ ወዝ አደር ቀስ በቀስ ቡርዧ እየሆነ ነው ፥ ይህም የሁሉም መንግሥታት ከፍተኛ ቡርዧ ዓላ ማው የቡርዧ መሥፍንነትንና የቡርዧ ወዝአደርነትን ከቡር ዧው ጋር ጐን ለጐን ለመያዝ ነው ። መላውን ዓለም

ለሚበዘብዝ አንድ መንግሥት ይህ አሠራር ከሞላ ጐደል ተቀባይነት ያገኛል ።» ከሩብ ምዕተ ዓመት ገደማ በኋላ ነሐሴ 11 ቀን 1881 ዓ. ም. ኤንግልስ « የማይረቡት የእንግሊዝ የሠራተኛ ማህበራት በመካከለኛው ለተ ሸጡ ወይንም የሱ ቅጥረኛ በሆኑ ሰዎች ራሳቸውን እንዲ መሩ ያደርጋሉ ። »ብሎ ተናግሯል ። መስከረም 12 1882 ዓ. ም. ለኮትስኪ በጻፈው ደብዳቤ ኤንግልስ « ስለ ቅኝ ግዛት ፖሊሲ የእንግሊዝ ሠራተኞች ምን እንደሚያስቡ ብትጠይቀኝ፣ ስለማንኛውም ፖለቲካ በአጠቃላይ ከሚያስ ቡት የተለየ አይደለም ። እዚያ ወግ አጥባቂዎችና ለዘ ብተኛ ሥርነቀሎች ብቻ እንጂ የሠራተኛ ፓርቲ ስለሌለ ሠራተኛው የእንግሊዝ የዓለም ዓቀፍ ሞኖፖሊና ቅኝ ግዛቶች ያስገኙትን ድግስ በደስታ ይካፈላል።»ይላል[108] ። (ኤንግልስ የሠራተኛው መደብ ሁኔታ በኢንግላንድ ለሚ ለው እትመት በጻፈው የመግቢያ ጽሑፍ ውስጥ ተመሣ ሣይ ሃሣቦችን አስፍሮ ነበር ።)

ይሄ ምክንያቶችንና ውጤቶችን ቁልጭ አድርጎ ያሣያል።ምክንያቶቹ/1/ ዓለም በዚህ አገር መበዝበዝ ፤ /2/የዚህ አገር በዓለም ገበያ ውስጥ ያለው የሞኖፖሊስት አቋም (3) የቅኝ ግዛታዊ ሞኖፖሊ ናቸው ። ውጤቶቹም (1) የእንግሊዝ ወዝአደር ጥቂት ክፍል ቡርዧ መሆን(2) የወዝ አደሩ ጥቂት ክፍል የቡርዧው ቅጥረኞች ወይንም እነሱ የገዟቸው እንዲመሩት ራሱን አሳልፎ መስጠት ናቸው ።

የሃያኛው ምዕተ ዓመት መጀመሪያ ኢምፔሪያሊ ዝም በእፍኝ ሙሉ መንግሥታት መካከል የዓለምን ክፍፍል ቀድሞውኑ ጨርሷል ፤ በ1858 ዓ. ም. እንግሊዝ ትበዘብዘው ከነበረው «የዓለም ክፍል» ጥቂት አነስ ያለ ውን እያንዳንዳቸው እንዲበዘብዙ ተከፋፍለዋል ፡ (ከነ

ዚህ ከፍተኛ ትርፍ ለማግኘት በሚመች መንገድ) ትረስቶች ካርቴሎች ፣ የገንዘባዊ ወረት የአበዳሪና ተበዳሪ ግንኙነት ምስጋና ይድረሳቸውና እያንዳንዱ መንግሥት በዓለም ገበያ የሞኖፖሊስት አቋም አግኝቷል ፤ እያንዳንዱ ባለቅኝ ግዛት ፤ ሞኖፖሊ ስላለው እስከ ተወሰነ ደረጃ ይደሰታል ። (ከዚህ በፊት እንዳየነው ከጠቅላላው 75,000,000 ኪ.ሜ.ካ የቅኝ ግዛት ስፋት ውስጥ 65,000,000 ኪ. ሜ. ካ. ወይ ንም 86 እጅ ከመቶው ስፋት የስድስት ኃያላን ይዞታ ነው። 61.000,000 ኪ. ሜ. ካ ወይንም 81 እጅ ከመቶ የሶስት ኃያላን ይዞታ ነው ።)

የአሁኑ ሁኔታ መለያ ባህርዩ ፣ በአድርባይነትና በሠ ራተኛው መደብ ንቅናቄ ጠቅላላና ወሳኝ ፍላጐት መካ ከል ያለውን የማይታረቅ ቅራኔ ሊያባብሱ የሚችሉት ፣ የምጣኔ-ሀብትና የፖለቲካ ሁኔታዎች ገኖ መታየት ነው ። ኢምፔሪያሊዝም ከእምቡጥነት ወደ ገናናነት ደረጃ ተሸጋግሯል ። ካፒታሊስት ሞኖፖሊዎች የምጣኔ ሀብ ቱንና የፖለቲካውን የመጀመሪያ ቦታ ይዘዋል ። የዓለም መከፋፈል ተጠናቋል ። በሌላ በኩል ደግሞ ቀድሞ ታላቋ ብሪታንያ ብቻ ያለተጋሪ ይዛው የነበረውን ሞኖፖሊ አሁን ጥቂት የኢምፔሪያሊስት ኃይሎች ድርሻቸውን ለማ ግኘት እየታገሉ ናቸው ። ይህም ትግል የመላው የሃያኛው ምዕተ ዓመት መጀመሪያ ወቅት ጠባይ ነው ። አሁን አድ ርባይነት በሠራተኛው መደብ ንቅናቄ ውስጥ ፣ በአሥራ ዘጠነኛው ምዕተ ዓመት አጋማሽ ላይ በእንግሊዝ ተደርጐ እንደነበረው ሙሉ በሙሉ በአሸናፊነት ሊወጣ አይች ልም ። ነገር ግን በርከት ባሉ ሃገሮች ውስጥ አድጐ ፣ በስሎ ከመብሰልም አልፎና በስብሶ ሙሉ በሙሉ ከቡርዧው ፖሊሲ ጋር «በሕብረተሰብ ትምህክተኝነት» ቅርጽ ተዋ ህዷል ። ★109

## ም ዕ ራ ፍ ዘ ጠ ኝ

# የኢምፔሪያሊዝም ግምገማ (ክሪቲክ ኦፍ ኢምፔሪያሊዝም)

አባባሉን በሰፊው ስንመለከተው የኢምፔሪያሊዝም ግምገማ ስንል የተለያዩ የኅብረተሰብ መደቦች ከጠቅላላው ርዕዮተ ዓለማቸው ጋር በማዛመድ ስለ ኢምፔሪያ ሊስት ፖሊሲ የሚኖራቸው አቋም ማለታችን ነው ።

በጥቂቶች እጅ የደለበውና በአንድ ወገን ትንሹንና መካከለኛውን ብቻ ሣይሆን በጣም ትንሽ ካፒታሊስቶች ንና ትንንሽ ጌቶችን በቁጥጥሩ ሥር የሚያውለውን የግን ኙነቶችና የዝምድናዎች ጥልቅና በሰፊው የተዘረጋ መረብ የሚፈጥር ፣ በሌላ ወገን ደግሞ ዓለምን ለመከፋፈልና ሌሎችን ሀገሮች በቁጥጥር ሥር ለማድረግ በሌሎች ብሔራዊ የገዢ መደቦችና በርካታ ባለገንዘቦች ላይ የከረረ ትግልን የሚፈጥር ገንዘባዊ ወረት፤ሃብት ያላቸው መደቦች ጭልጥ ብለው ከኢምፔሪያሊስት አምባ እንዲገቡ ያደርጋቸዋል ። «በሙሉ ልብ» ኢምፔሪያሊዝም ወደፊት ሊያስገኝ በሚ ችለው ተስፋ ከመጠን በላይ መደሰት ፣ በታላቅ ቁጣ ለሱ መቆምና በብሩህ ቀለም እሱን መቀባባት ፣ እነዚህ ናቸው የጊዜው ምልክቶች ። ኢምፔሪያሊስት ርዕዮተ ዓለም የሠርቶ አደሩን መደብ ጠልቆ ሊገባ ይችላል ። የቻይና ግንብ እንኳ ከሌሎች መደቦች ሊለያቸው አይችልም ። የጀርመን «ሶሻል ዲሞክራቲክ» ፓርቲ የዛሬ መሪዎች እየተባሉ የሚጠሩት « ሶሻል ኢምፔሪያሊስቶች » ፣ ማለትም በቃላት ኅብረተሰብአውያን በግብር ግን ኢም ፔሪያሊስቶች ፣ ተብለው መጠራታቸው ተገቢ ነው ። ይህም ሲሆን ሆብሰን ቀደም ብሎ በ1902 ዓ. ም. በእንግሊዝ

የአድር ባዩ የሩቢያን ኅብረተሰብ ወገን የሆኑ « ሩቢያን ኢምፔሪያሊስቶች » እንደ ነበሩ ጠቅሷል ።

የቡርዧ ምሁራንና ለሩፊዎቻቸው በጣም በጉዶሬ መንገድ ነበር ለኢምፔሪያሊዝም መቆጣቸውን የሚያሳውቁት ፤ ፍጹም የሆነ በሳይንቱንና እየጠለቀ የሚሔደውን ሥሩን ይጋርዳሉ ፣ ልዩ የሆኑትንና በሁለተኛ ደረጃ መታየት ያለባቸውን ነጥቦች ከፊት ለማስቀደም በመሞከር « ለጥገና » ባንኮች ወይም ቱሪስቶች በፖሊሲ መጠበቅ የመሳሰሉትን ፍጹም አስቂኝ ዕቅዶች በማቅረብ በጣም ጠቃሚ የሆኑ ነጥቦችን ከማየት ያግዳሉ ። የአንድ ነገር ጥሩነት የማይዋጥላቸውና ግልጽ የሆኑ ኢምፔሪያሊስቶች ማለትም የኢምፔሪያሊዝምን መሠረታዊ ጠባያትን ጠግኖ የማቅረብ ሐሣብ ምክንያት የለሽ እንደሆነ አምነው የሚቀበሉት አልፎ አልፎ የሚታዩ ክስተቶች ናቸው ።

አንድ ምሳሌ እንውሰድ ፣ የዓለም ምጣኔ ሀብት መዛግብት በሚለው መጽሔት ውስጥ የጀርመን ኢምፔሪያሊስቶች በቅኝ ግዛቶች ውስጥ ፣ የጀርመን ባልሆኑት ውስጥ ማለት ነው ፣ የሚካሔደውን የብሔራዊ አርነት ንቅናቄዎች ለመከታተል ይሞክራሉ ። በሕንድ ውስጥ ያለውን አለመረጋጋትና የቅዋሜ ንቅናቄዎች ፣ በናታል (ደቡብ አፍሪካ) ያለውን ንቅናቄ እንዲሁም በሆላንድ ምሥራቅ ኢንዲስ ፤ ወዘተ . . ይጠቅሳሉ ።

የበርካታ ተገዢ ብሔሮችና በውጭ መንግሥት ሥር የሚተዳደሩ የእስያ ፣ የአፍሪካና የአውሮፓ የሕዝብ ዝርያዎች ተወካዮች በ1910 ዓ. ም. ከሰኔ 28 — 30 አድርገውት ስለነበረው ስብሰባ ከእንግሊዝ በቀረበው ዘገባ ላይ ፣ ከነዚህም አንዱ ሲተች በስብሰባው ላይ የተደረጉትን ንግግሮች በማድነቅ እንዲህ ሲል ጽፏል ። « ኢምፔሪ

ያሊዝምን እንድንወጋ ፣ ስለነበረው ስብሰባ ከእንግሊዝ በቀረበው ዘገባ ላይ ፣ ከነዚሁም አንዱ ሲተች በስብሰባው ላይ የተደረጉትን ንግግሮች በማድነቅ እንዲህ ሲል ጽፏል ።

« ኢምፔሪያሊዝምን እንድንወጋ ፣ የተገዢ ሕዝቦችን ነጻ መውጣት ገዢ መንግሥታት ማወቅ እንዳለባቸው ፣ ዓለም አቀፍ የፍርድ ሸንጐ በታላላቅ ኃያላንና በደካማ ሕዝቦች መካከል የሚደረገውን ስምምነት በ ተቆጣጣሪነት እንዲመለከት መደረግ እንዳለበት ይነገረናል ። እነዚህ ሁሉ በእምነት የምንጠብቀውን ተስፋ ከመግለጽ አያል ፉም ። ኢምፔሪያሊዝም ከካፒታሊዝም ጋር በአሁኑ ቅርጹ የማይነጣጠል መሆኑን ፣ ስለሆነም ኢምፔሪያሊዝምን በይፋ መታገል ውጊያው በተለይ በአንዳንድ በሱ አስከፊ ትርፍራፊ ባሕርዮች ላይ በሚደረጉ ቅዋሜዎች ካልተወ ሰነ በስተቀር ተስፋ ቢስ መሆኑን ቅንጣት ታህል እንኳን መረዳት የተቻለ አይመስልም !![110]» የኢምፔሪያሊዝምን መሠረት መጠገን ማታለል ፣ « እምነታዊ ተስፋ » ስለ ሆነ ፣ የተጨቋኞቹ ብሔሮች ቡርዧ ተወካዮች « ወደፊት » ምንም ስለማይራመዱ ፣ የጨቋኙ ብሔር ቡርዧ ተወካዮች « ርቀው » ወደኋላ በመሔድ « ሣይንሣዊ » ነን በሚል ሽፋን ራሳቸውን ለኢምፔሪያሊዝም ያስገዛሉ ። ይህም ደግሞ « ሎጂክ » ነው !!

የኢምፔሪያሊዝምን መሠረት መጠገን መቻል አለ መቻል ፣ ኢምፔሪያሊዝም የሚያስከትላቸውን ተጻራሪ ነቶች የበለጠ ማፋፋምና ጥልቀት እንዲኖራቸው ወደ ፊት መቀጠል አለመቀጠል ፣ ወይንም እነዚህን ተጻራሪ ነቶች እንዲመነምኑ ለማድረግ ወደኋላ መመለስ አለመ መለስ የሚሉት ጥያቄዎች የኢምፔሪያሊዝም ግምገማ መሠረታዊ ጥያቄዎች ናቸው ። የኢምፔሪያሊዝም የተ ለየው ፖለቲካዊ ባሕርዩ በየትም ቦታ አድሃሪ መሆን

የገንዘባዊ ሥልጣን ጭቆናና የነጻ ውድድር መጥፋት ሥራ ላይ በመዋላቸው ምክንያት እየጨመረ የሔደው ብሔራዊ ጭቆና ስለሆነ ፥ በይበልጡ የኢምፔሪያሊስት ሀገሮች የንኡስ ከበርቴ ዲሞክራሲያዊ ቅዋሜ በኢምፔሪያሊዝም ላይ ፥ የተነሣው በሃያኛው ምዕተ ዓመት መግቢያ ላይ ነበር ። ኮትስኪ ይህንን በምጣኔ ሃብት መሠረቱ አድሃሪ የንዑስ ከበርቴ ጠጋኝ ቅዋሜ ለመቃወም አለመሞከሩ ወይንም ሊቃወም አለመቻሉ ብቻ ሳይሆን በግብርም ከነሱ ጋር ተዋህዷል ፤ እናም እዚህ ላይ ነው ኮትስኪና ሠፊው ዓለም አቀፋዊው ኮትስኪያን ዝንባሌ ማርክሲዝምን የከዳው ።

በተባበሩት አሜሪካ በ1898 ዓ. ም. በስፓኝ ላይ የተካሔደው የኢምፔሪያሊስት ጦርነት ፥ «የጸረ— ኢምፔሪያሊስቶችን ጦርነት» «ውንብድና» ብለው የጠሩትን ፥ የውጭ ግዛቶችን ማጠቃለልን የመንግሥቱን መመሪያ እንደመተላለፍ አድርገው የቆጠሩትን ፥ የፊሊፒኖዎቹን መሪ አጉናልዶ ( አሜሪካኖች በመጀመሪያ አገሩ ነጻ እንደምትወጣ ቃል ገብተውለት ነበር ፥ በኋላ ግን ቃላቸውን አጥፈው ወታደሮቻቸውን አስፍረው በግዛትነት አጠቃለሏት) የተፈጸመበት ድርጊት «የጅብደኛ ክዳት » ነበር ፥ ያሉትን የቡርዧ ዲሞክራሲ የመጨረሻ ሞሂካኖች ቅዋሜ ቀሰቀሰ ። እነዚሁ ሞሂካኖች የአብርሃም ሊንከንን ንግግር ሲጠቅሱ « ነጮች ራሳቸውን ሲያስተዳድሩ ራስን በራስ ማስተዳደር ይባላል ። ራሳቸውንና ሌሎችንም ሲያስተዳድሩ ግን ይህ ራስን በራስ ማስተዳደር ሣይሆን ጭቆና (ዲስፖቲዝም) ነው ።» ብለዋል[111] ። ይሁንና ይህ ሂስ በኢምፔሪያሊዝምና በትረስቶች ብሎም በኢምፔሪያሊዝምና በካፒታሊዝም መሠረቶች መካከል ያለውን የማይበጠስ ግንኙነት ከማስተዋል እስከ ተቆጠበ ድረስ የከፍተኛ መ

ጠን ካፒታሊዝምና ዕድገቱ ያስከተሏቸውን ኃይላት ከማ ገናዘብ እስከተቆጠበ ድረስ እምነታዊ ምኞት ሆኖ ይቀራል።

ይህ ስለ ኢምፔሪያሊዝም ባደረገው ግምገማ ላይ ሆብሰንም ወስዶት የነበረው ዋንኛው አዝማሚያ ነው ። ኮትስኪ « ኢምፔሪያሊዝም የማይቀር ስለመሆኑ » ተቃውሞ የሚተነሣውን ሀሣብና (በካፒታሊዝም ውስጥ ! ) የሕዝቡን «የመጠቀም ችሎታ መጨመር» አስፈላጊነት ደግፎ እንደሚከራከር ሆብሰን ገምቶ ነበር ። የኢምፔሪያሊዝምን ግምገማ አስመልክቶ ንዑስ ከበርቴዎች ስለ ባንኮች ኃያልነት ፥ ስለገንዘባዊ ሥልጣን ፤ ወዘተ ያላቸው አመለካከት ፥ ከዚህ በፊት በጠቀስኳቸው ደራሲያን እንደ አግሀድ ፥ ኤ ለንስበርግ ፥ ኤል ኤሽዌጅ እና ከፈረንሣይ ጸሐፊዎች ቪክቶር ቢራርድ ፥ የአንድ እንግሊዝና ኢምፔሪያሊዝም ፥ በሚል ርዕስ በ1900 ዓ. ም. የታተመ ጥልቀት የሌለው መጽሐፍ ደራሲ የመሳሰሉት ፥ ካላቸው ጋር ተመሳሳይ ነው ። እነዚህ ሁሉ ራሳቸውን ማርክሲስት ብለው የማይጠሩት ደራሲያን ፥ ኢምፔሪያሊዝምን ከነጻ ውድድርና ከዲሞክራሲ ጋር ያነጻጽራሉ ፥ወደ ግጭትና ጦርነት ፥ለሠላም ፍጹም «ግብረ ገባዊ»ምኞት ወደሆን፤ወዘተ.. የሚመራውን የባግዳድን የባቡር መሥመር እቅድም ያወግዛሉ ። ይኸው አባባል ፥ የዓለም አቀፋዊ ስቶክና አክሲዮን እዶላ ስታቲስቲኮችን ጠራዥ ለነበረው በ1912 ዓ.ም. « ዓለም አቀፋዊ » መተማመኛዎችን የሚያመለክተውን በሺህና በሚሊዮን የሚቆጠረውን ፍራንክ ሂሣብ ካሠላ በኋላ ፥ « ሠላም ይናጋል ፥ ይህንን ያህል ገንዘብ እያየ ጦርነት ለማስነሳት የሚቃጣ አለ ብሎ ማመን ይቻላልን ?»[112] ... ብሎ ላለው ለኢ. ኔይማርክም ያገለግላል።

የዚህ ዓይነቱ የአእምሮ ደካማነት (ከቡርዧ ኢኮኖሚስቶች ቢመጣ አያስደንቅም ። ከዚህም በላይ ይህን

ያህል የዋሕ ለመምሰል ቢሞክሩና በኢምፔሪያሊዝም ጊዜ ሠላም ይኖራል ብለው «አምረው» ቢያወሩ ለጥቅ ማቸው ሲሉ የሚያደርጉት መሆኑ መታወቅ አለበት ። በ1914፤1915 እና 1916 ዓመቱ ምሕረቶች ያንኑ የቡርዧ ጠጋኝነት አመለካከት በማንፃት ሠላምን አስመልክቶ «ሁሉም (ኢምፔሪያሊስቶች ፣ ሀሣዊ ሶሻሊስቶችና የኅብ ረተሰብአዊ እርቅ ፈላጊዎች) የተስማሙበት ነው » ብሎ ሲል የቱ ዘንድ ነው የኮትስኪ ማርክሲዝም? ኢምፔሪያሊ ዝምን በሙትንቱን ፈንታና የቅራኔዎቹን ሥረ መሠረት በማጋለጥ ፋንታ የተደረገ ነገር ቢኖር እነሱን ማግለል ፣ ከነሱ መሸሽ ፣ የጠጋኝ « ግብረገባዊ ምኞት » ነው ።

ኮትስኪ ስለኢምፔሪያሊዝም ካደረገው ምጣኔ ሀብ ታዊ ሂስ ለናሙና የሚከተለውን እንውሰድ ። የእንግሊ ዝን ከግብጽ ጋር የማስመጣትና የመላክ ንግድ ላው ውጥ የ1872ን እና 1912ን ይወስዳል፤ ይህ የማስመጣትና የመለክ የንግድ ልውውጥ ከእንግሊዝ ጠቅላላ የውጭ ንግድ ያነሰ እያዘገመ ያደገ ይመስላል ። ኮትስኪ ከዚህ « በወታደራዊ ኃይል በመያዝ ባይሆን ኖሮ እንግሊዝ ከግ ብጽ ጋር የነበራት ንግድ በቀላሉ በምጣኔ—ሀብታዊ ሁኔ ታዎች አስገዳጅነት ይቀጥል ነበር ፣ ብለን ለማለት ምንም ማስረጃ አይኖረንም» ብሎ ይደመድማል ። «የወረት መስፋፋት በኢምፔሪያሊዝም አመጻዊ ዘዴዎች ሣይሆን በሠላማዊ ዲሞክራሲ በተሻለ መንገድ ሊራመድ ይችላል ።»[113]

በሩሲያዊው ጋሻ ጃግሬው (ሕብረተሰባዊ ትምክህ ተኛ ሩሲያዊው መካች)' በሚስተር ስፔክታር በያመቱ የተደጋገመው የኮትስኪ አባባል የኮትስኪያንን የኢምፔ ሪያሊዝም ግምገማ መሠረት ይይዛል ፣ ስለሆነም ነው ሠፋ ባለ አኳኋን መተንተን የሚያሻን ፣ ማጠቃለያውን

ኮትስኪ በየጊዜው በተለይም በሚያዝያ ወር 1915 ዓ.ም. « መላ የኅብረተሰብአዊ ንድፈ ሀሣባውያን በአንድ ጊዜ እንደራሳቸው ሃሣብ አድርገው የተቀበሉት » ብሎ ከሚ ያውጅለት ከሂልፈርዲንግ በመጥቀስ እንጀምራለን ።

« ይህ የወዝ አደሩ ጉዳይ አይደለም » ይላል ሂልፈር ዲንግ ሲጽፍ « የበለጠ ተራማጅ የሆነውን የካፒታሊስት ፖሊሲ ጊዜው ካለፈበት የነጻ ንግድና ለመንግሥት ካለው ጠላትነት ጋር ማነጻጸር ለገንዘባዊ ወረት ፣ ለኢምፔሪያ ሊዝም ፣ ምጣኔ ሀብታዊ ፖሊሲ ወዝአደሩ ያለው መልስ ነጻ ንግድ ሣይሆን ኅብረተሰብአዊነት ነው ። ዛሬ የወዝ አደሩ ፖሊሲ ዓላማ ነጻ ውድድርን መልሶ ለመሠየም ሃሳባዊ መሆን አይችልም ። ይህ በአሁኑ ጊዜ ፀረ ተራማጅ ሃሳባዊ ሆኗል ። ውድድርን ፈጽሞ ማጥፋትና ካፒታሊዝምን መደምሰስ እንጂ ። »[114]

በገንዘባዊ ወረት ከፍተኛ የታሪክ ወቅት « ጸረ ተራ ማጅ ሀሳባዊ» ፣ « ሠላማዊ ዲሞክራሲ»፤ «የምጣኔ ሀብት ሁኔታዎች መሥራት ብቻ» እያለ በማስተጋባት ፣ ኮትስኪ ጭልጥ ብሎ ከማርክሲዝም ተገንጥሎ ይወጣል ፣ ምክን ያቱም በነባራዊ ሁኔታ ይህ ሀሳባዊ ከሞኖፖሊ ካፒታሊ ሊዝም ወደ ኢሞኖፖሊ ካፒታሊዝም መልሶ ይወስደናል። ስለዚህም የጠጋኝ ማጭበርበር ነው ።

ከግብጽ ጋር ንግድ (ከማንኛውም ቅኝ ግዛት ወይንም ከፊል ቅኝ ግዛት) ፤ በወታደራዊ ኃይል አስገድዶ በመያዝ ሣይሆን ፣ ካለ ኢምፔሪያሊዝም ፣ እንዲሁም ገንዘባዊ ወረት ሣይኖር ፣ «ሊያድግ ይችል ነበር» ። ይህ ምን ማለት ነው ? ነጻ ውድድር ፣ በአጠቃላይ በሞኖፖሊዎች ፣ ወይ ንም በገንዘባዊ ወረት « የግንኙነቶች » ቀንበር (ማለትም የሞኖፖሊዎችም ጭምር) ፣ ወይንም በአንዳንድ ሀገሮች ቅኝ ግዛቶችን በሞኖፖሊነት መያዝ ፣ ታፍኖ ባይያዝ

ኖሮ ካፒታሊዝም በተሟጠነ አኳኋን ሊዳብር ይችል ነበር ለማለት ነው ?

የኮትስኪ ክርክር ሌላ ትርጉም የለውም ፤ ይህ ትርጉም « ትርጉም » የለሽ ነው ። ነጻ ውድድር ፣ ካለአንዳች ዓይነት ሞኖፖሊ ፣ ካፒታሊዝምንና ንግድን ሊያዳብር ይችል ነበር እንበል ፣ ነገር ግን የካፒታሊዝምና የንግድ በተፋጠነ ሁኔታ ማደግ ፣ የምርትንና የወረትን ድልበት የበለጠ ያሳድገዋል ። ይህም በተራው ለሞኖፖሊ መፈጠር ምክንያት ይሆናል ። እናም ሞኖፖሊዎች ከነጻ ውድድር ወጥተው በትክክለኛው አድገዋል ። ምንም እንኳን ሞኖፖሊዎች አሁን ዕድገትን መግታት ቢጀምሩም ለሞኖፖሊ ሥፍራውን ከለቀቀ በኋላ ተመልሶ ሊመጣ ለማይችለው ለነጻ ውድድር የመከራከሪያ ነጥብ ሊሆን አይችልም።

የኮትስኪን አባባል በየትኛውም በኩል ብናገላብጠው ፣ የምናገኘው ጸረ ተራማጅነትንና ቡርዧ ጠጋኝነትን ብቻ ነው ።

ስፔክታቶር እንዳለው ይህንን አባባል ብናሻሽለውም እንኳ ማለትም የቅኝ ግዛቶች ከሌሎች ሃገሮች ጋር ካላቸው የንግድ ግንኙነት ይልቅ ከእንግሊዝ ጋር ያላቸው ንግድ በጣም በዝግታ ነው የሚያድገው ብለን ብንልም እንኳን ኮትስኪን የሚያድነው አይሆንም ፤ ምክንያቱም ታላቋ ብሪታንያን በውድድር የሚያሸንፏት የሌላ ሀገር (አሜሪካ ፣ ጀርመን) ሞኖፖሊና ኢምፔሪያሊዝም ናቸውና። ካርቴሎች ለአዲስና ልዩ ዓይነት ለሆነ የከሰል ታሪፍ መፈጠር ምክንያት መሆናቸው የታወቀ ነው ፣ ማለትም ለውጭ ንግድ የሚውሉ ዕቃዎች ከፍተኛ ጥበቃ ይደረግላቸዋል ። (ኤንግልስ በካፒታል ቅጽ 3 ውስጥ ይህንን ጠቅሶታል ) ። ካርቴሎችና የገንዘባዊ ወረት « ዕቃዎችን በቅናሽ ተመን ወደውጭ የመላክ » ወይንም እንግሊዞች

እንደሚሉት « ማራገፍ » የራሳቸውን የሆነ ልዩ ሥርዓት እንዳላቸውም የታወቀ ነው ። ባገር ውስጥ ካርቴል ዕቃ ዎችን በከፍተኛ የሞኖፖሊ ተመን ሲሸጥ በውጭ ሀገር ግን ተወዳዳሪውን ለመጣል የራሱን ምርት እስከመጨ ረሻው ለማስፋት ፤ ወዘተ . . . ሲል በጣም ቅናሽ በሆነ ተመን ይሸጣል ። ከእንግሊዝ ቅኝ ግዛት ሀገሮች ጋር ያለው የጀርመን ንግድ እነዚሁ ሀገሮች ከእንግሊዝ ጋር ካላቸው ይልቅ በፍጥነት ቢዳብር ፥ የሚያረጋግጠው የጀርመንን ኢምፔሪያሊዝም ወጣትነት ፥ ጠንካራና የበላይ ከሆነው ከእንግሊዝ ኢምፔሪያሊዝም ይልቅ በተሻለ አኳኋን የተደራጀ መሆኑን ነው ። ይሁን እንጅ በምንም አኳኋን የነጻ ንግድ ፥ በከለሳና በጠጋኝነት መካከል የሚደረግ ትግል ሣይሆን በተቀናቃኝ ሁለት ኢምፔሪያሊዝሞች፥ ሁለት ሞኖፖሊዎች ፤ ሁለት የገንዘባዊ ወረት ወገኖች መካከል የሚካሔድ እንጂ።የጀርመን ኢምፔሪያሊዝም በእንግሊዝ ኢምፔሪያሊዝም ላይ ያለው « የበላይነት » ከቅኝ ግዛት ጠረፍ ግድግዳ ወይንም ከከለሳ ታሪፍ የበለጠ ጠንካራ ነው ። ነጻ ንግድና « ሠላማዊ ዲሞክራሲን » ለመደገፍ ፥ ይህንን እንደመከራከሪያ ነጥብ አድርጎ ማቅ ረብ ርካሽነት ነው ። የኢምፔሪያሊዝምን ጠቃሚ ባሕር ያትና መለያዎች መዘንጋት ፥ ማርክሲዝምን በንዑስ ከበ ርቴ ጠጋኝነት መተካት ማለት ይሆናል ።

ስለማርክሲዝም ያቀረበው ሂስ ልክ እንደ ኮትስኪው ሁሉ ንዑስ ኮበርቴ የሆነው ፥ የከበርቴ ኢኮኖሚስት ኤ. ለንስበርግ ፥ ስለ ንግድ ስታትስቲክስ ያደረገው ጥናት ወደ ሣይንሣዊነት የበለጠ የተጠጋ መሆኑን ማስታወስ ጠቃሚ ነው ። በዘፈቀደ የተመረጠን አንድ ሀገር ወይንም አንድን ቅኝ ግዛት ከሌሎች ሀገሮች ጋር አላወዳደረም ፥ የአንድን ኢምፔሪያሊስት ሀገር የውጭ ንግድ መርምሮ

(1) በገንዘብ በኩል ጥገኛዋ ከሆኑትና ገንዘብ ከሚበደሩት (2) በገንዘብ በኩል ጥገኛ ካልሆኑ ሀገሮች ጋር በማወዳደር የሚከተለውን ውጤት አግኝቷል ።

የጀርመን የውጭ ንግድ (በሚሊዮን ማርክ)

በጀርመን ላይ የገንዘብ ጥገኛ ለሆኑ ሀገሮች

| | 1889 | 1908 | በመቶ ጭማሪ |
|---|---|---|---|
| ሩማንያ . . . . . . | 48.2 | 70.8 | 47.0 |
| ፖርቹጋል . . . . . | 19.0 | 32.8 | 73.0 |
| አርጀንቲና . . . . . | 60.7 | 147.0 | 143.0 |
| ብራዚል . . . . . . | 48.7 | 84.5 | 73.0 |
| ቺሊ .. . . . . . . | 28.3 | 52.4 | 85.0 |
| ቱርክ . . . . . . | 29.9 | 64.0 | 114.0 |
| ድምር | 234.8 | 451.5 | 92.0 |

በጀርመን ላይ ገንዘባዊ ጥገኝነት በሌላቸው ሀገሮች

| | | | |
|---|---|---|---|
| ታላቋ ብሪታንያ . . . | 651.8 | 997.4 | 53 |
| ፈረንሣይ . . . . . | 210.2 | 437.9 | 108 |
| ቤልጅግ . . . . . | 137.2 | 322.8 | 135 |
| ስዊዘርላንድ . . . . | 177.4 | 401.1 | 127 |
| አውስትሪያ . . . . . | 21.2 | 64.5 | 205 |
| ሆላንድ ምሥራቅ ኢንዱስ | 8.8 | 40.7 | 363 |
| ድምር | 1206.6 | 2264.4 | 87 |

ላንስበርግ ማጠቃለያ አላቀረበም ፤ ስለዚህም የሚያስገርመው ቁጥሮቹ የሚያስረዱት አንዳች ነገር ካለ የሱን ልክ አለመሆን ብቻ መሆኑን ሊረዳ አለመቻሉ ነው ። ምክንያቱም በመጠኑም ቢሆን በገንዘባዊ መንገድ በጀርመን ላይ ጥገኛ ካልሆኑት ሀገሮች ጋር ከነበረው የውጭ ንግድ ይልቅ ከጥገኛ ሀገሮች ጋር የነበረው የውጭ ንግድ ግንኙ

ነት በተፋጠነ መንገድ አድጓል ። («ካለ» የሚለውን ቃል ጠበቅ ያደረግሁት የላንስበርግ ቁጥሮች ያልተሟሉ በመ ሆናቸው ነው ።)

በውጭ ንግድና በብድር መካከል ያለውን የግንኙ ነት ፈለግ በመከተል ላንስበርግ ሲጽፍ ፥ « በ1890—91 አንድ የሩማንያ ብድር ፥ ባለፉት ዓመታት ይህንኑ ብድር ባበረከቱ የጀርመን ባንኮች ፥ እንዲተላለፍ ተደርጐ ነበር። ይህም ብድር በይበልጥ የባቡር መሥመር ዕቃዎች ከጀ ርመን ለመግዛት ሥራ ላይ ውሎ ነበር ። በ1891 ወደ ሩማ ንያ የገባው የጀርመን ዕቃ 55 ሚሊዮን ማርክ ነበር ። በሚ ከተለው ዓመት ወደ 39.4 ሚሊዮን ማርክ ሲወርድ ፥ እየ ዋዠቀ በ1900 ወደ 25.4 ሚሊዮን ማርክ ዝቅ ብሏል ። የሁለቱ አዲስ ብድሮች ምሥጋና ይግባቸውና በቅርብ ዓመ ታት ብቻ ነበር የ1891 ዓ. ም. አቋማቸውን ላይዙ የቻ ሉት ። » ወደ ፖርቱጋል የሚላኩት የጀርመን ዕቃዎች ከ1888 — 89 ብድር በኋላ ፥ ወደ 21.1 ሚሊዮን (1890) ከፍ አሉ ፤ ከዚያ በኋላ በሚከተሉት ሁለት ዓመታት ወደ 16.2 ሚሊዮንና 7.4 ሚሊዮን ዝቅ ብለው በ1903 ዓ.ም. ነው የቀድሞው ደረጃቸውን የያዙት ።

« ከአርጀንቲና ጋር ያሉት የጀርመን ንግድ መጠን አሀዞች አሁንም የበለጠ የሚያስደንቁ ናቸው ። በ1888 ና 1890 ብድሮች ተጠየቁ ፥ ወደ አርጀንቲና የሚሄዱት የጀርመን ውጤት ዕቃዎች 60,700,000 ማርክ (1889) ደረሱ ። ከሁለት ዓመታት በኋላ ወደ 18.600,000 ማርክ ፥ ከላይ ከተሰጠው አሀዝ ከአንድ ሶስተኛ እጅ በታች ወረዱ ። ከ1901 በኋላ ፥ ያውም አዲስ ብድር በመንግሥትና በመዘጋጃ ቤቶች ለኃይል ማመንጫ ጣቢያዎች ለማቋቋ ምና ለሌሎችም የዱቤ ግልጋሎቶች ፥ ከተገኙ በኋላ ነው

የውጭ ንግዶቹ ተመን የ1889ን ተመን በማለፍ አዲስ ደረጃ የደረሰው ።

« በ1889 ዓ. ም. በተሰጠው ብድር ምክንያት ወደ ቺሊ የሚገባው የጀርመን የውጤት ዕቃዎች መጠን ወደ 45,200 000 ማርክ ከፍ ብሏል (1892) ። ከአንድ ዓመት በኋላም ወደ 22,5000,000 ማርክ ወረደ ። የጀርመን ባንኮች በ1906 የሠጡት አዲስ ብድር የውጭ ንግዱን መጠን በ1907 ወደ 84,700,000 ማርክ ከፍ ሲያደርገው ፣ በ1908 ተመልሶ በመውረድ ወደ 52,400,000 ዝቅ ብሏል ።[115]

ከነዚህ እውነታዎች ላንስበርግ ፣ ንግድ ከብድር ጋር ከተያያዘ ምን ያህል ያልረጋና የተዛባ እንደሚሆን ፣ የሀገርን ውስጥ ኢንዱስትሪ « በተቀናባበረና » « መሆን ባለበት መንገድ » በማስፋፋት ፈንታ ወረትን በውጪ አገር እንዲሠራ ማድረግ ምን ያህል መጥፎ እንደሆን ፣ የውጭ ብድር ለመስጠት መቆሸሽ መልክ ክፋፕ የሚከ ፍለው በሚሊዮን የሚቆጠር ማርክ ምን ያህል « ውድ እንደሆን » ወዘተ . . . በመዘርዘር አስቂኙን የንዑስ ከበ ርቴ ሞራል ጨምቆ ያወጣል ። ይሁን እንጂ እውነታዎቹ በትክክል የሚያስረዱን ፣ የውጭ ንግድ መጨመር ከገን ዘባዊ ወረት ማጭበርበርና ማታለል ጋር በትክክል የተያ ያዙ መሆናቸውን ሲሆን ፣ ገንዘባዊ ወረት ስለ ቡርዧ ሞራ ሊቲ ግድ ኖሮት ሳይሆን በሬውን ዳግም ለመግፈፍ በመ ጀመሪያ የብድሩን ትርፍ ወደ ኪሱ ይከታል ፣ ከዚያም በኋላ ደግሞ ከዚያው ተበዳሪው ከክፋኝ ግዢ ለማድረግ ወይንም የባቡር መስመር ቁሳቁሶች ከአረብ ብረት ሲን ዲኬት ለመግዛት ወዘተ . . . ከተበደረው ገንዘብ ሌሎች ትርፎችን ወደ ኪሱ ለመከተት ነው ፣ የሚጥረው ።

የለንስበርግ አሀዞች በምንም ዓይነት የተሟሉ ናቸው ብዬ አለማጤኔን ደግሜ ማሣወቅ እፈልጋለሁ ። ይሁን

እንጂ ከኮትስኪና ከስፔክቴተር አሀዞች የተሻለ ሣይ ንሣዊ ስለሆኑና ሳንስበርግ ወደ ጥያቄዎቹ ለመቅረብ ትክክለኛውን መንገድ ስለተከተለ የሱን አሀዞች መጥቀስ ይኖርብኛልና ነው ። የውጭ ንግዶችን ፤ ወዘተ እስመልክቶ ስለ ገንዘባዊ ወረት ዓይነተኛነት ለመወያየት የውጭ ንግድ ከባለ ገንዘቦች ሥውር ዶባ በተለይና ለብቻ በካርቴሎች ዕቃዎችን መሸጥ ፤ ወዘተ . . . ያላቸውን የተለየና ብቸኛ ግንኙነት ነጥሎ ማየት ያስፈልጋል ። ቅኝ ግዛቶችን ቅኝ ግዛቶች ካልሆኑ ሀገሮች ፤ አንዱን ኢምፔሪያሊዝም ከሌላው ፤ አንዱን ከፊል ቅኝ ግዛት ወይንም ቅኝ ግዛት (ግብፅ) ከሁሉም ሌሎች ሀገሮች ጋር በቀላሉ ማወዳደር የጥያቄውን ውስጣዊ ባሕርይ ማጨለምና ከሱም መሸሽ ይሆናል ።

ስለ ኢምፔሪያሊዝም ሂስ የኮትስኪ ንድፈ ሐሣብ ከማርክሲዝም ጋር ምንም ግንኙነት የሌለው ከመሆኑም በላይ ከአድርባዮችና ከሶሺያል ትምክህተኞች ጋር ለሠላምና ለአንድነት ፕሮፓጋንዳ መግቢያ ነው ። የኢምፔሪያሊዝምን በጣም ጥልቅ የሆነውንና መሠረታዊውን ቅራኔ ፣ ጐን ለጐን የሚገኙትን የሞኖፖሊንና የነጻ ውድድርን ፣ የገንዘባዊ ወረትን ግዙፍ « አሠራርና» (ግዙፍ ትርፍም) « ሀቀኛ » ንግድ በነጻ ገበያ ቅራኔዎች ፣ ካርቴሎችና ትረስቶች ፣ በአንድ ወገንና ካርቴላዊ ያልሆነ ኢንዱስትሪ በሌላ ወገን ሆነው ያላቸውን ቅራኔ ፤ ወዘተ . . . ያጨልማል ፣ ያሸሻል ።

በኮትስኪ የተፈለሰፈው መደዴው የ« ላዕለ ኢምፔሪያሊዝም» ንድፈ ሀሣብም ይህንኑ ያህል አድሃሪ ነው። በ1915 ዓ. ም. በዚሁ ርዕስ ላይ የነበረውን አባባል በ1902 ሆብሰን ከነበረው አባባል ጋር እናወዳድር ።

ኮትስኪ ፡— « . . የአሁኑ ኢምፔሪያሊስት ፖሊሲ ፣ እርስ በእርስ በሚፎካከሩ ብሔራዊ ገንዘባዊ ወረቶች ቦታ በዓለም አቀፋዊ የገንዘባዊ ወረት አንድነት የዓለምን መበዝበዝ በሚያመጣው ፣ በአዲሱ ልዕለ ኢምፔሪያሊዝም ሊተካ አይችልም ? ለማንኛውም ይህ አዲስ የካፒታሊዝም ደረጃ በምንም የማይቀር ነው ። ሊደረስበት ይቻላልን ? ይህን ጥያቄ ለመመለስ በቂ መሠረት የለንም ።»[116]

ሆብሰን ፡— « እያንዳንዱ ፡ ካልሠለጠኑ ጥገኛ ተከታዮች ጋር በጥቂት ታላላቅ ፌዴራል ግዛት አጼዎች ውስጥ የተዘረጉት የክርስቲያን ሀገሮች (ክርስቲያን ዶም) ፣ ለብዙዎች የጊዜው ሒደት በጣም ትክክለኛ የሆነ ዕድገትና ለዘላቂ ሠላም የተሻለ ተስፋን በኢምፔሪያሊዝም መካከል የተረጋገጠ መሠረት ፡ የሚሰጥ ይመስላቸዋል ። »

ከአሥራ ሶስት ዓመታት በፊት ሆብሰን የኢምፔሪያሊዝም አንድነት ብሎ የገለጸውን ኮትስኪ ልዕለ — ኢምፔሪያሊዝም ወይንም ከፍተኛው — ኢምፔሪያሊዝም ብሎ ይጠራዋል ። አዲስና ብልህ አቀንቃኝ ቃላት ከመፈልሰፉ በስተቀር አንዱን የላንቲን መነሻ በሌላ ከመተካቱ በስተቀር « በማይንማዊ » አስተሳሰብ አድማስ ኮትስኪ ያደረገው እርምጃ ፣ ሆብሰን በመሠረቱ የእንግሊዝ ቀሳውስት ምፅድቅና ብሎ የገለጠውን ፣ እሱ እንደማርክሲዝም ማቅረቡ ብቻ ነው ። ከእንግሊዝና ደች ጦርነት በኋላ፣ በደቡብ አፍሪካ ጦር ሜዳ ብዙ ወገኖቻቸውን ያጡትንና ለእንግሊዝ ባለገንዘቦች የበለጠ ከፍተኛ ትርፍ ለማስገኘት ብዙ ግብር የመክፈል ግዴታ ያለባቸውን የእንግሊዝን መካከለኛ መደብና ሠራተኛውን ለማጽናናት ከፍተኛ ጥረት ማድረግ ፣ ለነዚህ በከፍተኛ ደረጃ የተከበሩ ለየት ያሉ የኅብረተሰብ ወገኖች የተለመደ ነበር ። ኢምፔሪያሊዝም ይህን ያህልም መጥፎ አይደለም ፣ ዘላቂ ሠላ

ምን ወደሚያረጋግጠው አንድነት (ወይንም ልዕለ) ኢምፔ ሪያሊዝም ጠጋ ብሎ ይገኛል ፣ ብሎ ከማለት የተሻለ ምን ማፅናኛ ይኖራል ? የእንግሊዝ ቀሳውስት ወይንም የኮት ስኪ ሞኙ ስሜት መልካም ሀሣብ ምንም ቢሆን ፣ « የኮ ትስኪ ንድፈ ሀሣብ » ብቸኛ ነባራዊ ፡ ማለትም ትክክለኛ ኅብረተሰብአዊ ጠቃሚነት ሀሣባቸውን ካከረረው ቅራ ኔና ከተፋፋመው የጊዜው ችግር በማገለል ፣ የሐሣብ ነጸ ብራቅ ወደሆነው የወደፊቱ «ልዕለ ኢምፔሪያሊዝም» የቅዥት ተስፋ ሀሣባቸውን በመምራት ፣ ለሠፊው ሕዝብ በካፒታሊዝም ውስጥ ዘላቂ ሠላም እንደሚቻል ተስፋ የመስጠት አድሃሪ የማፅናኛ ዘዴ ነው ። ሠፊውን ሕዝብ ማታለል ! ይህ ብቻ ነው በኮትስኪ « የማርክሲስት ንድፈ ሀሣብ » ውስጥ ያለው ።

በእርግጥ ኮትስኪ በጀርመን ሠራተኞች (የመላው ዓለም ሠራተኞች) ፊት ስለማያጭበረብርበት ተስፋ ፍጹም ፋርሽነት የሚያወላውል እምነት ላይ ለመድረስ የታወ ቁና አሌ የማይባሉ እውነታዎችን ማወዳደር ይበቃል ። ሕንድን ፣ ኢንዶ ቻይናና ቻይናን እናጢን ። ከስድስት እስከ ሰባት መቶ ሚሊዮን ሕዝብ የሚኖራቸውን ሶስት ቅኝ ግዛትና ከፊል ቅኝ ግዛት ሀገሮች ፣ በብዙ ኢምፔሪያሊስት ኃያላን ታላቋ ብሪታንያ ፣ ፈረንሣይ ፣ ጃፓን ፣ ዩናይትድስ ቴትስ ፤ ወዘተ . . . ገንዘባዊ ወረት ብዝበዛ ሥር የወደቁ መሆናቸው የታወቀ ነው ። እነዚህ ኢምፔሪያሊስት ሀገሮች በነዚህ እስያዊ መንግሥታት ላይ ያላቸውን የተፅዕኖ አካባቢ ፣ ፍላጐትና ይዞታ ለማስፋፋትና ለመከ ላከል እያንዳንዳቸው ስምምነት ላይ ይድረሱ እንበል ። ይህ ስምምነት « የኢምፔሪያሊዝም አንድነት» ወይንም «የልዕለ ኢምፔሪያሊዝም» ውህደት ይባላል ። ሁሉም ኢምፔሪያሊስት ሀገሮች ይህንን የእስያን ክፍል በሠ ላም ለመከፋፈል አንድ ዓይነት ስምምነት ላይ ይደ

ርሳሉ እንበል ። ይህ ስምምነት « በዓለም አቀፋዊ ደረጃ የተዋሀዶ የገንዘባዊ ወረት ስምምነት » ይባላል ። በሃያኛው ክፍለ ዘመን ታሪክ ውስጥ የዚህ ስምምነት ምሳሌዎች ተፈጽመዋል ። ኃያላኑ ስለቻይና የወሰዱት አቋም ለምሳሌ — የካፒታሊስት ሥርዓት እንዳለ ይቆይ እንበል — ኮትስኪም ይሕንኑ አባባል ነውና የሚለው እንዚህ ስምምነቶች ከጊዜያዊነት አልፈው ፍትጊያ ፣ ግጭትንና ፣ ትግልን ሊያስቀሩ ይችላሉ ብሎ መገመት «ይቻላልን? » ብለን እንጠይቃለን ።

ጥያቄው ግልጽ ባለ አኳኋን ሙቅረብ ያለበት ከአሉታ በስተቀር ለማንኛውም ዓይነት መልስ ማግኛ መሆን የለበትም ። ምክንያቱም በካፒታሊዝም ወቅት ፣ የተጽእኖ አካባቢዎችን ፣ ፍላጐቶችን ፣ ቅኝ ግዛቶችን ፣ ወዘተ . . ለመከፋፈል መነሻ ይሆናል ተብሎ ሊገመት የሚችለው የተካፋዮቹን ኃይል ፣ ማለትም ጠቅላላ የምጣኔ — ሀብታዊ ፣ ገንዘባዊና ወታደራዊ ኃይል ፣ ወዘተ . . . ተንትኖ መረዳት ነው ። በዚህም ላይ በከፍያው የተካፋዮቹ ኃይል ተመጣጣኝ ለውጥ ሊይዝ አይችልም ፣ ምክንያቱም በካፒታሊዝም ወቅት ፣ የተስተካከለ የድርጅቶች ፣ ትረስቶች ፣ የኢንዱስትሪ ቅርንጫፎች ፣ ወይንም የሀገሮች ፣ መዳበር ሊኖር አይችልምና ። ከግማሽ ምዕተ ዓመት በፊት የካፒታሊስት ኃይሏ በጊዜው እንግሊዝ ከነበራት የካፒታሊስት ኃይል ጋር ሲወዳደር ፣ ጀርመን ችግረኛ ፣ እዚህ ግቢ የማትባል ሀገር ነበረች ። ጃፓንም ከሩሲያ ጋር ስትወዳደር እንደዚሁ ። በአሥርና በሃያ ዓመታት ጊዜ ውስጥ የኢምፔሪያሊስት ኃይላት አንጻራዊ ኃይል ምንም ሣይለወጥ ይቆያል ብሎ « መገመት » ይቻላልን ? አይታሰብም ።

ስለዚህ በካፒታሊስት ሥርዓት እውነታዎች ውስጥ የእግሊዝ ቀሣውስትም ሆነ የጀርመኑ « ማርክሲስት »

የኮትስኪ መደዴ ፈሪሣዊ ቅዠቶች ውስጥ ሣይሆን ፣ «የኢምፔሪያሊስቶች አንድነት » ወይንም « ልዕለ — ኢምፔሪያሊስት » ሕብረት ፤ ምንም ዓይነት ቅርጽ ይኑራቸው ፤ የአንዱ ኢምፔሪያሊስት ከሌላው ማጣመር ወይንም ሁሉንም ኢምፔሪያሊስቶች ኃያላን የሚያቅፍ ጠቅላላ የሕብረት ስምምነት ፤ በጦርነቶች ወቅት ከሚደረጉ « የጦርነት ማቆም » ስምምነቶች ሌላ ምንም ሊሆኑ አይችሉም ። ሠላማዊ የሕብረት ስምምነቶች ለጦርነቶች መንገድ ይጠርጋሉ ፤ እነዚህ በተራቸው ከጦርነቶች ውስጥ ወጥተው ያድጋሉ ። በአንዱ ፤ የኢምፔሪያሊስት ዝምድናዎችና በዓለም ምጣኔ ሀብታዊና ፖለቲካዊ ግንኙነቶች ውስጥ ባለው መሠረት ላይ የሚደረግ ሠላማዊና ሠላማዊ ያልሆነ የትግል ቅርጽ በመለዋወጥ አንደኛው ለአንደኛው መኖር አስፈላጊ ይሆናል ። ሠራተኛውን ለማረጋጋትና ወደ ቡርዧው ከድተው ከገቡት የሶሺያል ትምክህተኞች ጋር ለማስታረቅ ፤ ብልጡ ኮትስኪ የሠንሠለቱን አንደኛውን ክፍል ከሌላ ያላቅቃል ፤ ሁሉም ኃያላን « በቻይና መረጋጋትን » ለመፍጠር (የቦክሰሩን አመጽ መታፈን እናስታውስ) አሁን የሚያደርጉትን ሠላማዊ (እናም ልዕለ ኢምፔሪያሊስት ፤ ልዕለ ኢምፔሪያሊስት አይደለም) የሕብረት ስምምነት ፤ ሠላማዊ ካልሆነው የነገው ግጭት እንበል ከነገ ወዲያ ቱርክን ለመቀረማመት ለሚያስችል ሌላ « ሠላማዊ » አጠቃላይ የሕብረት ስምምነት መንገድ ከሚጠርገው ፤ ይለያል ፤ ወዘተ ፣ ወዘተ . . . ። በኢምፔሪያሊስቱ የጦርነት ጉዞና በኢምፔሪያሊስቱ የሠላም ጊዜ መካከል ያለውን ሕያው ዝምድና በማቅረብ ፈንታ ኮትስኪ ፣ ሙታን ከሆኑ መሪዎቻቸው ጋር እርቅ እንዲያደርጉ ለሠራተኞቹ ሙት የሆነውን ማፈግፈግ ይጋብዛቸዋል ።

የዲፕሎማሲ ታሪክ በአውሮፓ በአለም አቀፋዊ መስፋፋት ሂደት ውስጥ በሚለው መጽሐፍ ውስጥ ከአሜ ሪካዊው ጸሐፊ ሂል ፤ በመግቢያው ላይ ቀጥሎ ስለተመ ለከቱት የዲፕሎማሲ ታሪክ ወቅቶች ጠቅሷል ። (1) የአ ብዮት ዘመን (2) ሕገ መንግሥታዊ ንቅናቂ (3) የአሁኑ ዘመን «የንግድ ኢምፔሪያሊዝም» ።[117] ሌላ ጸሐፊ ከ1870 ዓ. ም. ወዲህ የነበረውን የእንግሊዝን « የዓለም ፖሊሲ» በአራት ክፍሎ አቅርቦታል ። (1)የመጀመሪያው የእስያ ወቅት) ሩሲያ በማዕከላዊ እስያ ወደ ህንድ የምታደርገ ውን እንቅስቃሴ ለመግታት ይደረግ የነበረው የትግል ወቅት) (2) የአፍሪካ ወቅት ( በግምት ከ1885 — 1902) ፥ አፍሪካን ለመቀራመት ከፈረንሣይ ጋር ይደረግ የነበረው ትግል ወቅት (ከፈረንሣይ ጋር ጦርነት ሊጀምሩ ጥቂት ቀርቷ ቸው የነበረው 1898 «የፋሾዳዊ ግጭት») (3) ሁለተኛ የእስያ ወቅት (ሩሲያን ለማጥቃት ከጃፓን ጋር ሕብረት ማድረግ ፡) እና (4) «የአውሮፓውያን» ወቅት[113] በይበልጥ ጸረ—ጀር መን ። «በገንዘባዊ መስክ የፖለቲካ ቃፊሮች ግጭቶች ይደረ ጋሉ» ብሏል ፤ ባንከኛው ሪየስር ፤ በ1905 ፤ በኢጣሊያን ሀገር ይሠራ የነበረው የፈረንሣይ ገንዘባዊ ወረት በሁለቱ ሀገሮች መካከል የፖለቲካ የጋራ ስምምነት ለመፍጠር እንዴት አድርጐ መንገድ ያዘጋጅ እንደነበረ እና ፐርሺያን (አሁን ኢራንን) ለመያዝ ጀርመንን የታላቋ ብሪታንያ ፥ የቻይናን ብድር አስመልክቶ ደግሞ በመላው የአውሮፓ ካፒታሊስ ቶች መካከል ግጭት እንዴት እየተስፋፋ እንደሄደ ለማ ሳየት በጻፈው ጽሑፍ ውስጥ «የሠላማዊ ልዕለ ኢምፔሪያ ሊስት » የጋራ ስምምነቶች ከማናቸውም የኢምፔሪያሊ ስት ግጭቶች ጋር ያላቸውን የማይበጠስ ግንኙነት የሚያ ሳየውን ይህን ያህል ሐቅ ተመልከቱት ! !

ኢምፔሪያሊዝምን በብሩህ ቀለም በመቀባት ሌላ ምንም ሊሆን የማይችለው ያኮትስኪ በኢምፔሪያሊዝም

ውስጥ ያሉትን ሥር የሠደዱ ቅራኔዎች ለማጨለም መሞ
ከር ፣ ይህ ደራሲ ስለ ኢምፔሪያሊዝም ፖለቲካዊ ገጾች
ያቀረበው ሂስ ውስጥ ተሰልክቷል ። ኢምፔሪያሊዝም
ለነጻነት ሳይሆን ለተፅዕኖ ጥረት የሚያደርግ የሞኖፖሊ
ዎችና የገንዘባዊ ወረት ከፍተኛ ወቅት ነው ። ኢምፔሪያ
ሊዝም ምንም ዓይነት የፖለቲካ ሥርአት ይሁን ውጤቱ
የነዚህ አዝማሚያዎች ውጤት በየትም ቦታ ጸረ ተራማ
ጅና በዚህ መስክ የቅራኔዎች ከመጠን በላይ መፋፋም
ይሆናል ። በተለይ የሚበረታው የብሔራዊ ጭቆና ቀን
በርና የግዛት ማጠቃለል ጥረት ማለትም የብሔር ነጻነትን
መጻረር ጥረት (የግዛት ማጠቃለል ማለት የብሔሮችን
የራስን ዕድል በራስ የመወሰንን መብት መጻረር ነውና
ነው) ። በኢምፔሪያሊዝምና የብሔራዊ ጭቆና መፋፋም
መካከል የለውን ዝምድና ሲጠቅስ ሂልፈርዲንግ በትክ
ክል አስታውሷል ፡ «አዲስ በተገኙት ሀገሮች ውስጥ»
ይላል ሲጽፍ « ከውጪ የመጣው ወረት ቅራኔውን
ከማጧጧፉም ሌላ ንቃታቸው ከጊዜ ወደ ጊዜ በብሔራዊ
ደረጃ እየገፋ የሚሄደውን ሕዝብ የመቋቋም ኃይል ይቀ
ሠቅሣል ። ይህ መቋቋም በቀላሉ በውጭ ወረት ላይ አደ
ገኛ እርምጃን ሊያስወስድ የሚችል ነው ። የቀድሞው የኅ
ብረተሰብ ግንኙነቶች ሙሉ በሙሉ ይለዋወጣሉ ፣ ለዘ
መናት የቆየው የታሪክ አልባ ብሔሮች ከገጠር መለየት
ፈጽሞ ይጠፋና ፣ ብሔሮቹ በካፒታሊስት አዙሪት ውስጥ
ይገባሉ ። ለተገኙዎቹ እርነት መውጫ የሚያሻቸውን
ሁሉ ካፒታሊዝም ራሱ ቀስ በቀስ እያዘጋጀ ስለሚሔድ
አንድ ጊዜ ለአውሮፓ ብሔሮች ከፍተኛ መስሎ ታይቶ
የነበረውን ማለትም ለምጣኔ ሀብታዊና ለባህል ነጻነት
ማግኛ ይበጃል የተባለውን የኅብረት ብሔራዊ መንግሥት
የመፍጠርን ግብ ለመምታት ታጥቀው ይነሣሉ ። ይህ የብ
ሔራዊ ነጻ አውጪ ንቅናቄ የአውሮፓውያንን ወረት በጣም

ጠቃሚ በሆነውና ተስፋ በሚጣልበት የብዝበዛ መስክ ሥጋት ላይ ይጥለዋል ። ስለሆነም የአውሮፓ ወረት የተፅዕኖ ዕድሜውን ሊያረዝም የሚችለው የወታደር ኀይሉን ሳያቋርጥ በማሣደግ ነው ። »[119]

እዚህ ላይ ሊታከል የሚገባው ነገር ኢምፔሪያሊዝም ፣ አዲስ በተገኙት ሀገሮች ብቻ ሣይሆን በቀድሞዎችም በሥሩ ወደማጠቃለል የበለጠ ብሔራዊ ጭቆና ወደ ማሳደር ብሎም የሕዝቡን የመቋቋም ኀይል ወደመሣደግ ማምራቱ ነው ። የኢምፔሪያሊዝምን ፖለቲካዊ አድሃሪነት መክረር ቢያወግዝም ፣ ኮትስኪ አንድን በተለይ አንገብጋቢ የሆነ ጥያቄ ሸፋፍኖ ይተወዋል ። ይህም በዘመን ኢምፔሪያሊዝም ከአደርባዮች ጋር አንድነት ለመፍጠር ያለመቻሉ ጉዳይ ነው ። የግዛት ማጠቃለልን ቢቃወምም ፣ ቅዋሚውን አድርባዮች ሊቀበሉት በሚችሉትና እነሱን በማያስቀይም አኳኋን ያቀርበዋል ። ሃሣቡን ለጀርመን ሕዝብ ነው የሚያቀርበው ፣ ይሁን እንጂ ለመወያያ ርዕስ ሊሆን የሚችለውንና ጠቃሚውን ነጥብ ፣ ይህን የአልሣክሎሬይን በጀርመን መያዝ ፣ ያጨልማል ። ይህንን የኮትስኪን «የአእምሮ መቃወስ » በተሻለ መንገድ ለማቅረብ የሚከተለውን ምሳሌ እወስዳለሁ ። አንድ ጃፓናዊ አሜሪካ ፊሊፒንስን መያዟን ያወግዝ እንበል ። ጥያቄው ግን ይህን የሚያደርገው የሰውን ሃገር መያዝ አስከፊነት ተሰምቶት ሣይሆን ለራሱ ፊሊፒንስን ሣይዝ በመቅረቱ ተቆጭቶ ሊሆን ስለሚችል ምን ያህል ተደማጭነት ያገኛል ? ነው ። ከዚህም በላይ ኮርያ ከጃፓን እንድትገነጠል ፣ ነጻ እንድትሆን ፣ ካልጐተጐተና የኮርያን በጃፓን መያዝ ካልተዋጋ ፤ ይህ ጃፓናዊ በግዛት ማስፋፋት ላይ የሚያውጀው « ጦርነት » ሀቀኛና በፖለቲካዊ መንገድ እውነተኛ ነው ብለን ከመቀበል አንቆጠብምን ?

ስለኢምፔሪያሊዝም የሠጠው ንድፈ ሃሣባዊ ትን ተና ፣ እንዲሁም ደግሞ ኢምፔሪያሊዝምን በሚመለ ከት የሰጠው ምጣኔ — ሀብታዊና ፖለቲካዊ የኮትስኪ ሂስ ከማርክሲዝም ጋር ፈጽሞ ከማይታረቀው የኢምፔ ሪያሊዝምን መሠረታዊ ቅራኔዎች በማጨለምና በማደ ብዘዝ መንፈስና በአውሮፓ የሠራተኛ መደብ ንቅናቄ ውስጥ እየተፍረከረከ ያለውን የአድርባዮች አንድነት ለማሠንበት በሚደረግ ጥረት በጥልቀት እየተቦረቦሩ ናቸው

## ምዕራፍ አሥር

## በታሪክ ውስጥ ኢምፔሪያሊዝም የሚኖረው ሥፍራ ፤

በምጣኔ — ሀብታዊ ባሕሪው ኢምፔሪያሊዝም ሞኖ ፖሊ ካፒታሊዝም እንደሆነ ተመልክተናል ። ይህ ራሱ በታሪክ ውስጥ የሚይዘውን ሥፍራ ይወስናል ፤ ምክንያቱም ከነጻ ውድድር ግሕጸን ውስጥ ፣ በትክክልም ከነጻ ውድ ድር ውስጥ ወጥቶ የሚያድገው ሞኖፖሊ ፣ ከካፒታሊስት ወደ ከፍተኛ የሕብረተሰብ ምጣኔ ሀብታዊ ሥርዓት መሸ ጋገሪያ ነው ። በምናጠናው ወቅት መለያ የሆኑትን አራ ቱን ዋና ዋና የሞኖፖሊ አይነቶች ወይንም ዋና ዋና፤ የሞ ኖፖሊ ካፒታሊዝም ጠባዮችን በጥሞና መመልከት ያሻ ናል ።

በመጀመሪያ ፣ ሞኖፖሊ ፣ የምርት ድልበት ከፍተኛ ደረጃ ከመድረሱ የተነሳ የመጣ ነው ። ይህም የሞኖፖሊ ካፒታሊስት ማሕበሮችን ፣ ካርቴሎችን ፣ ሲንዲኬቶች ንና ትረስቶችን ይጠቅሳል ። እነዚህም በአሁኑ ጊዜ የም ጣኔ ሀብታዊ ሕይወት ውስጥ ምን ያህል ጠቃሚ ሚና እንደሚጫወቱ ተመልክተናል ። በሃያኛው ምዕተ ዓመት

መግቢያ ላይ በሠለጠኑት ሀገሮች ሞኖፖሊ ፍጹም የበላይነትን ተቀዳጅቶ ነበር ። እና ምንም እንኳን ካርቴሎችን ለማቋቋም በከፍተኛ ታሪፍ ጠለላ ያሉ ሀገሮች (ጀርመን ፣ አሜሪካ) የመጀመሪያ እርምጃ የወሰዱ ቢሆንም ፣ ታላቋ ብሪታንያ ፣ በነጻ ንግድ ሥርዓቷ ፣ ጥቂት ቢዘገይም ፣ ተመሳሳይ መሠረታዊ ክስተትን ፣ ማለትም ከምርት ድልበት የሞኖፖሊን መወለድ አስተዋውቃለች።

ሁለተኛ ፣ ሞኖፖሊዎች በካፒታሊስቱ ኅብረተሰብ ውስጥ ላሉት በተለይም አዲስ ለሚቋቋሙትና በጣም ከፍተኛ በሆነ ደረጃ ካርቴላዊ ለሆኑት ኢንዱስትሪዎች ለከሠልና ለብረት ኢንዱስትሪዎች ፡—የሚያስፈልጉት ጥሬ ዕቃዎች የሚገኙባቸውን ምንጮች የመያዝ ከፍተኛ ጉጉት አሳደሩ ። በጣም ጠቃሚ የሆኑ የጥሬ ዕቃዎች ምንጮች ሞኖፖሊ ፣ የትልቅ ወረትን ኃይል ከመጠን በላይ አሳድጓል ፤ እንዲሁም ካርቴላዊ በሆኑና ካርቴላዊ ባልሆኑ ኢንዱስስትሪዎች መካከል ያለውን ተጻራሪነት አትብቶታል ።

ሶስተኛ ፣ ሞኖፖሊ ከባንኮች ተስፈንጥሮ የወጣ ነው። ባንኮች ከተራ የአቀባባይ ድርጅቶች ወደ ገንዘባዊ ወረት ሞኖፖሊስቶች እየዳበሩ መጡ ። በእያንዳንዱ ቀደምትነት ባላቸው የካፒታሊስት ሀገሮች ውስጥ ያሉ ከሶስት እስከ አምስት ታላላቅ ባንኮች በኢንዱስትሪያዊና በባንክ ወረት መካከል መቆላለፍ «ፈጥረዋል» ። በተጨማሪም የመላ ሀገሮችን ገቢና ወረት ከፍተኛውን እጅ የሚይዘውን በሺና በሺህ ሚሊዮን ብር የመቆጣጠር ሥልጣን በመዳፋቸው ውስጥ አስገብተዋል ። ያለምንም ምርጫ በመላ የጊዜው ምጣኔ ሀብታዊና ፖለቲካዊ ተቋሞች ላይ በዘመኑ የቡርዧ ሕብረተሰብ የጥገኝነት ግንኙነቶች መረቡን የሚዘረጋው ገንዘባዊ ሥልጣን ነው—እንዲዚህ ነው ይህ አስደናቂው ሞኖፖሊ የሚንጸባረቀው ።

አራተኛ ፣ ሞኖፖሊ ከቅኝ ግዛት ፖሊሲ ውስጥ ነው ወጥቶ የዳገው ። በአያሌ « የጥንት » የቅኝ ግዛት ፖሊሲ ዓላማዎች ላይ ገንዘባዊ ወረት የጥሬ ዕቃ ምንጮችን ለማ ግኘት ወረት ወደ ውጪ ለመላክ ፣ በተፅእኖ ክልል ማለትም ትርፍ የማግኛ ስምምነቶቹ ፣ የሞኖፖሊ ትርፎች ፤ ወዘተ.. በአጠቃላይ በምጣኔ ሀብት ግዛቶች ፣ መታገልን አክሎ በታል ። ለምሳሌ በአውሮፓ ኃያላን ተይዘው የነበሩት ቅኝ ግዛቶች የአፍሪካ አንድ አስረኛ በነበሩበት ወቅት (በ1876 ዓ ም. እንደነበረው) የቅኝ ግዛት ፖሊሲ ይሰሩ የነበ ረው በሞኖፖሊ ሳይሆን ያገኙትን ግዛት « በማግበስበስ» ነበር ። ይሁንና የአፍሪካ ዘጠኝ አሥረኛው ከተያዘ በኋላ (1900) ፣ መላው ዓለም ከተከፋፈለ በኋላ ማለት ነው ፣ የማይቀረው ቅኝ ግዛቶችን በሞኖፖሊ መያዝ ዘመን መጣ፣ ብሎም ዓለምን ለመከፋፈልና መልሶ ለመከፋፈል የተ ጧጧፈ ትግል የማካሔጃው ጊዜ ተጀመረ ።

ሞኖፖሊያዊ ወረት በካፒታሊዝም ውስጥ ያሉትን ቅራኔዎች በምን ደረጃ እንዳከረራቸው በአጠቃላይ ይታ ወቃል ። የኑሮ ውድነትንና የካርቴሎችን ጭቆና በምሳሌ ነት መጥቀስ በቂ ይሆናል ። ይህ የቅራኔዎች መክረር ፣ ከአለም አቀፍ ገንዘባዊ ወረት የመጨረሻ ድል በኋላ መሥ ራት የጀመረውን ከፍተኛውን የታሪክን የመሸጋገሪያ ወቅት አሽከርካሪ ኃይል ይይዛል ።

ሞኖፖሊዎች ፣ የጥቂቶች ባለገንዘብ ሥልጣን መያዝ ለነጻነት ሳይሆን ለጭቆና ጥረት ማድረግ ፣ ቁጥራቸው እየ ጨመረ የሚሔድ ትንንሽና ደካማ መንግሥታት በእፍኝ ሙሉ ኃብታምና ኃያላን መንግሥታት ተፅእኖ ሥር እን ዲወድቁ ጥረት ማድረግ ፣ እነዚህ ሁሉ ጥባቴ ወይንም እየ በሰበሰ የሚሔድ ብለን እንድንጠራው የሚያስገድዱን የኢምፔሪያሊዝም መለያ ጠባያት መንሥኤዎች ናቸው። ከ

ኢምፔሪያሊዝም አዝማሚያዎች እንደ አንዱ ሆኖ ፣ ቡርዧው ከ—እስከ እያደገ በሚሔድ ደረጃ ወረቱን ወደውጪ በመላክና « ኩፖኖችን በመቁረጥ » በሚያገኘው ገቢ የሚኖርበት የአራጣ አበዳሪ መንግሥት ፣ የወለድ ሰጭ መንግሥት መፈጠር ብቅ ይላል ። የመበስበሱ አዝማሚያ የካፒታሊዝምን በተፋጠነ አኳኋን ማደግ ያስቀራል ብሎ ማመን ስህተት ይሆናል ። አያስቀርም ። በኢምፔሪያሊዝም የታሪክ ሒደት ወቅት ፣ አንዳንድ የኢንዱስትሪ ቅርንጫፎች ባንዳንድ የቡርዧ ክፍሎችና አንዳንድ አገሮች ይብዛም ይነስ በተለያየ መጠን ፣ አንድ ጊዜ የአንዱን አዝማሚያ ሌላ ጊዜ ደግሞ የሌላውን አዝማሚያ በመከተል ይከዳሉ። በአጠቃላይ ፣ ካፒታሊዝም ከበፊቱ በጣም በተፋጠነ አኳኋን ነው የሚያድገው ። ይሁን እንጂ ይህ አስተዳደግ የበለጠ የተዛባም ብቻ አይሆንም ፣ መዛባቱም በተለይ በወረት በበለጸጉ አገሮች (እንግሊዝ) መበስበስም ይከሰታል ።

የጀርመንን ምጣኔ ሀብት በፍጥነት መዳበር በሚመለከት ፣ ስለጀርመን ታላላቅ ባንኮች የተጻፈው መጽሐፍ ደራሲ ሪየዘር እንዲህ ይላል ።

« ልክ ፣ በጣም ከመፍጠኑ የተነሳ በመንገዱ ላይ የሚያጋጥሙትን ሠላማዊ እግረኞችን ብቻ ሳይሆን በውስጡ የሚጓዙትንም ለአደጋ ከሚያጋልጠው የአሁኑ ጊዜ አውቶሞቢል ፣ የጥንቱ ደብዳቤ አመላላሽ ጋር እንደሚወዳደረው ሁሉ ፣ እንደዚሁም በትክክል አዝጋሚ ነበር ለማለት የማይቻለው ያለፈው ጊዜ እርምጃም (1848—70) ከጠቅላላው የጀርመን ብሔራዊ ምጣኔ—ሀብትና ከሱም ጋር የጀርመን የባንክ ሥራ ፈጣን ዕድገት ጋር (1870—1905) ሊወዳደር ይችላል ። « ይህ ከመጠን በላይ በሆነ ፍጥነት ያደገው ገንዘባዊ ወረት በበኩሉ ሊነጠቁ የሚችሉትን ቅኝ ግዛቶች « በተረጋጋ አኳኋን» (በሰላማዊ መን

ገድ ብቻ ሳይሆን) ሀብታም ከሆኑ ሀገሮች ወደ መንጠቁ ይሸጋገራል ። በዩናይትድ ስቴትስ ባለፉት የአሥር ዓመ ታት ወቅቶች ውስጥ የተደረገው የምጣኔ ሀብት ዕድገት በጀርመን ተደርጎ ከነበረውም በጣም ፈጣን ነበር ። ስለሆነም ነው የዘመኑ የአሜሪካ ካፒታሊዝም ጥባታዊ ባሕርያት አፍጥጠውና አግጥጠው የማታዩት ። በሌላ በኩል ደግሞ ፣ እንበል የሪፐብሊካን አሜሪካዊ ቡርዧ ከዘውድ አገዛዙ ጃፓናዊ ወይንም ጀርመናዊ ቡርዧ ጋር ሲወዳደር በኢምፔሪያሊዝም ወቅት ጐልቶ የሚታየው የፖለቲካ ልዩነት ዝቅተኛ ደረጃ ይዞ ይታያል ፤ ጠቃሚ ሣይሆን ቀርቶ እስከአሁን የተነሱት ጉዳዮች ሁሉ የሚመ ለከቱት የተወሰነ የጥባቴአዊነት ባሕርያት ያለውን ቡርዧ ስለሆነ ነው ።

ከብዙዎቹ የኢንዱስትሪ ቅርንጫፎች ከአንደኛው ፤ ከብዙዎቹ ሀገሮች ከአንደኛው ፤ ወዘተ ካፒታሊስቶቹ የሚ ቀበሉዋቸው ከፍተኛ የሞኖፖሊ ትርፎች ፣ የሠራተኛ ውን የተወሰኑ ክፍሎች ለጊዜው ቢሆንም በቀላሉ የማይገ መቱትን በጉቦ ለመደለልና ወደ አንድ የተወሰነ የኢን ዱስትሪ ወይንም የብሔር ቡርዧዎች ለማቅረብ ያስችላ ቸዋል ። ዓለምን ለመከፋፈል በኢምፔሪያሊስት መንግ ሥታት መካከል የሚፋፋሙት ቅራኔዎች ይህንን ፍላጎት ከፍ ያደርጉታል ። ከዚህ በኋላ የኢምፔሪያሊስት ማደግ አንዳንዱ ባህርያት ፣ ከሌሎች ሀገሮች በቅድሚያ የታዩ ባት እስዋ በመሆኗ ፣ በታላቋ ብሪታንያ በመጀመሪያ በግ ልጽ እራሱን ያጋለጠው ፣ በኢምፔሪያሊዝምና በአድር ባይነት መካከል ያለው መተሣሰር ይፈጠራል ። አንዳንድ ጸሐፊዎች ፣ ለምሳሌ ኤልማርቶስ ፣ በሠራተኛው መደብ ንቅናቄ ውስጥ በተለይ በአሁኑ ወቅት አፋጦ ያለውን ሐቅ — በኢምፔሪያሊዝምና በአድርባይነት መካከል

ያለውን ግንኙነት ፤ የሚከተለውን አይነት « ይሩ የወደ ፊት ብሩህ ተስፋ» (ለኮትስኪና ለሁይስማንስ ወዮ!) ጠለላ በመውሰድ ገሸሽ አድርገው የማለፍ በሽታ አለባቸው ። አድርባይነትን የሚያሳድገው ተራማጅ ካፒታሊዝም ከሆነ ወይም ደህና ክፍያ የሚከፈላቸው ሠራተኞች ከሆኑ ወደአ ድር ባይነት የሚአዘነብሉት፤ወዘተ … የካፒታሊዝም ተቃዋ ሚዎች የተቃውሞ ሠንሾ ተስፋ ቢስ ይሆናል ። ስለእንደ ዚህ አይነቱ «የወደፊት ብሩህ ተስፋ» ምንም ውዥንብር ውስጥ ልንገባ አንችልም ። ከአድርባይነት አንጻር ያለ የወደፊት ብሩህ ተስፋ ነው ። አድርባይነትን ለመጋ ረድ የሚያገለግል ብሩህ ተስፋ ነው ? እንደ እውነቱ ከሆነ የአድርባይነት ዕድገት ከመጠን በላይ ፈጣን መሆንና የተለየ ዓመታዊ ጠባይ ያለው መሆኑ ለድል አድራጊ ነቱ ዘላቂነት ዋስትና ሊሠጡ አይችሉም ። በጤናማ ሠውነት ላይ ፈጥኖ የሚያድግ የእባጭ በሽታ ፈጥኖ በመ ፈንዳት ለህመምተኛው እፎይታን እንደሚያስገኘው ሁሉ ማለት ነው ። በዚህ አኳያ ከሁሉ የበለጠ አደገኞች የሚ ሆኑት ፣ ኢምፔሪያሊዝምን ከአድርባይነት ገንጥሎ መዋ ጋት ምን ያህል ከንቱ እንደሆነ ለመረዳት ፍላጎት የሌላ ላቸው ናቸው ።

እንግዲህ ፣ እስከአሁን በዚህ መጽሐፍ ውስጥ ስለኢ ምፔሪያሊዝም የምጣኔ ሀብት ባሕርይ ፣ በተባለው ላይ በመመሥረት ፣ ኢምፔሪያሊዝምን ፣ በመሸጋገሪያ ላይ ያለ ካፒታሊዝም ወይንም የበለጠ ትክክለኛ በሆነ መን ገድ (ሞቱ የተቃረበ) ካፒታሊዝም ብለን ለመጥራት እን ችላለን ። የአሁኑን ጊዜ ካፒታሊዝም ለመግለጽ ፣ የቡርዧ ኤኮኖሚስቶች ፣ እንደ « የሚያስተሣሥር » « መለያየት የሌለበት » ወዘተ . . . የመሳሰሉትን ግቀንቀኛ ቃላትንና ሐረጐች አዘውትረው እንደሚጠቀሙ ልብ ግለቱ ጠቃ

ሚ ትምህርት ያስገኛል ። በተጨማሪም « የሚሰጡት አገልግሎትና የዕድገት ሒደታቸው እንደሚያረጋግጠው » «ባንኮች የግል ሥራ ተቋሞች ብቻ አይደሉም ፥ ከጊዜ ወደ ጊዜ የግል ሥራ ሕግን አካባቢ ቀድመው እያደጉነው» የሚሉ ሀረጎችንም ይጠቀማሉ ። አባባሉን አሁን የጠ ቀስኩት ይኸው ሪዘር ራሱ ፥ ኮስተር ብሎ « ሕብረተሰብ አዊ ማድረግን» በሚመለከት የማርክሲስቶች « ትንቢት» « አልተፈጸመም ! » ይላል ።

ታዲያ ይህ «የሚያስተሳስር» የሚለው ጊዜያዊ ማቀ ንቀኛ ቃል ምንድነው የሚገልጸው ? እሱ የሚገልጸው በጣ ም ስሜትን የሚነካውን በጊዜያችን ሲፈጸም የምናየውን ባህርይ ነው ። ተመልካቹ ልዩ ልዩ ዛፎችን መቁጠር ሲችል እንጨቱን ግን ለማየት አለመቻሉን ያሳያል ። ጥልቀት የሌለውን ፤ ድንገተኛውን ፤ ምሥቅልቅሉን ፤ በጣም አስ ከፊ በሆነ አኳኋን ገልብጦ ያቀርባል ። ተመልካቹ በጥሬ ዕቃው ክምር ግራ እንደተጋባና ምንነቱንና ጥቅሙን በፍ ጹም ለመገንዘብ እንደማይችል አድርጎ ያቀርበዋል ። የአክሲዮኖች ባለቤትነት ፤ በግል ባለንብረቶች መካከል ያለ ግንኙነት «በዘፈቀደ መተሣሠር ነው» ። ነገር ግን ከዚህ መተሣሠር ሥር ፤ መሠረቱ ማለት ነው ፤ የሚለዋወጡት የምርት የህብረተሰብ ግንኙነቶች ይገኛሉ ። አንድ ትልቅ ድርጅት ከፍተኛ መጠን ሲይዝና ፤ በትክክለኛ ብዙ መረጃ አማካይነት ቀዳሚ ጥሬ ዕቃዎችን ዕደላ በእቅዱ መሠረት እስከ ሁለት ሶስተኛ ወይንም ሶስት አራተኛ እጅ ለአሥር ሚሊዮን ሕዝብ በሚያስፈልገው ሁሉ ሲያደራጅ፤ ጥሬ ዕቃ ዎች ሁሉ ሥነ ሥርዓት ባለውና በተደራጀ መንገድ ፤ አንዳንድ ጊዜ በመቶና በሺህ የሚቆጠሩ ማይሎች ወደሚራ ራቁ ፤ በጣም አመቺ ወደሆኑ የማምረቻ ሥፍራዎች ሲጓጓ ዙ ፤ አንድ ማዕከላዊ አካል ፤ ዕቃው ከመጀመሪያው ጀምሮ

አያሌ የተለያዩ ያለቁ ቁሳቁሶች ተመርተው እስከሚወጡ በት ደረጃ ድረስ ያለውን የሥራ ቅደም ተከተል እስከመ ራው ድረስ ፤ እነዚህ ምርቶች ሁሉ በአንድ ነጠላ ዕቅድ አማካይነት ለአሥርና ለመቶ ሚሊዮን ተጠቃሚ ህዝብ (በአሜሪካ የዘይት ትረስት አማካይነት ዘይት በአሜሪካና በጀርመን እንዲሸጥ ማድረግ ፤) እንዲከፋፈሉ ሲደረግ ፤ ከዚህ በኋላ ማምረት ህብረተሰብአዊ እንጂ እንዲያው ዝም ብሎ «መተሳሰር» ብቻ እንዳልሆነ ግልጽ ይሆናል ። የግል ምጣኔ — ሀብታዊና የግል ባለቤትነት ግንኙነቶች ፤ በው ስጡ የሚይዘውን አሁን ካለው በላይ ሊጨምር በማይችል ፤ መወገዱ ሰው ሠራሽ በሆነ መንገድ ከዘገየ መበስበሱ የማይ ጠረጠር ፤ በበሰበሰ አኳኋን ረዘም ላለ ጊዜ ሊቆይ በሚችል (እጅግ ቢበዛ የአድርባይነት እባጭ መዳን እንዲዘገይ ከተ ደረገ) ይሁን እንጂ መወገዱ በማያጠራጥር ፤ የውጪ ሽፋን ይመሰረታሉ ።

«ለጀርመን ኢምፔሪያሊዝም ከፍተኛ አድናቆት የነ በረው ሹልዝ—ጋቨርኒትዝ ቀጥሎ ያለውን ብሏል ።

«አንድ ጊዜ የጀርመን ባንኮች ከፍተኛው አመራር በጥቂት ግለሰቦች እጅ ገብቶ ነበር ፤ አሠራራቸው ዛሬ ፤ ለመንግሥቱ ሚኒስቴሮች ላብዛኛው ከሚሰጡት አገልግ ሎት ይልቅ ለሕዝበ የሚሰጡት የጐላ እንዲሆን አድር ጓል » (እዚህ ላይ ባንከኞች ፤ የሚኒስቴሮች ፤ የኢንዱስትሪ ማሕበሮችና የአራጣ አበዳሪዎች መተሳሰር ይሁንኝ ተብሎ ተረስቷል ።) «ከላይ የተጠቀሱትን አዝማሚያዎች ዕድገት እስከ ህጋዊ ፍጻሚያቸው ድረስ በአእምሮአችን ለማያዝ ብንሞክር የምናገኘው ፤ የብሔሩ የገንዘብ ወረት ፤ በባንኮች ውስጥ ተዋህዶ ፤ ባንኮቹ ራሳቸው በካርቴሎች ተጣምረው ፤ የብሔሩ ወረት ወጪ በመተማመኛ መልክ ተመድቦ ነው ። ከዚህ በኋላ የታላቁ አዋቂ ሴይንት ሳይ

መን ትንቢታዊ አስተሳሰብ ይፈጸማል ። የተስተካከለ ሆግ ሣይኖራቸው ከሚያድጉት የምጣኔ ሀብታዊ ግንኙነቶች ሀቅ ጋር የሚስማማው የአሁኑ ጊዜ የምርት ሥርዓተ አልባ ነት ፤ ለተቀናጀ ምርት ቦታውን ይለቃል ። አንዱ በሌላው ላይ ጥገኛ ሣይሆንና የሰውን ልጅ ምጣኔ—ሀብታዊ ፍላጐት ከግምት ውስጥ ሳያስገባ ፤ ምርት ከእንግዲህ ወዲህ በተለያዩ አፈብሪካዎች አይመራም ። ይህ በአንድ ሕዝባዊ ድርጅት የሚደረግ ነው ። አንድ ከፍተኛ ሥፍራን ከያዘ የአመለካከት ነጥብ ሠፊውን የኅብረተሰብ ምጣኔ—ሀብት ለመቆጣጠር የሚችል ማዕከላዊ የአመራር ኮሚቴ ለመላው ህብረተሰብ ጥቅም እንዲያመች አድርጎ ያስተካክለዋል ፤ የማምረቻ መሣሪያዎች በተፈላጊ ሰዎች ቁጥጥር ሥር እንዲውል ከማ ድረጉም በላይ በምርትና በግልጋሎት መካከል የማይለወጥ አንድነት እንዲኖር ለማድረግ ጥንቃቄ ያደርጋል ። አንድ ዓይነት ምጣኔ-ሀብታዊ የሥራ ቅንብር መኖሩን የመቆጣጠ ር አገልግሎት የሚሰጡ ድርጅቶች አሁንም ተቋቁመው ይገኛሉ ። እነዚህም ባንኮች ናቸው ። ከሴይንት—ሳይመን ትንቢት ብዙ ርቀን ነው ያለ ነው ፤ ይሁን እንጂ ወደዚያው እያዘገምን ነው ። ማርክሲዝም ማርክስ አስቦት ከነበረው በቅርጽ ብቻ ይለያያል ።

ይህ ማርክስን[120] አንኮታኩቶ «መቃወም» በርግጥም ከማርክስ ትክክለኛ ሳይንሣዊ ትንታኔ ወደ ሴይንት—ሳይመን የግምት ሥራ ፤ የአዋቂ የግምት ሥራ ፤ ይሁን እንጂ ያው ግምታዊ ሥራ ነው ፤ አንድ እርምጃ የሚያፈ ገፍግ ነው ።

## የግርጌ ማስታዎሻዎች

1 ከጀርመን አጼ የታሪክ መዝገብ የተወሠዱ አሀዞች ፡ 1911 ፡ ዘ ሀን

2 ዩናይትድ ስቴትስ ፡ የስታቲስቲክስ ግጠቃለያ 1912 ገጽ 202

3 ገንዘባዊ ወረት ፡ የሩሲያ እትም ፡ ገጽ 286—87

4 ሀንስ ጊዲዮን ሄይግን ፡ በጀርመን ትልቅ የብረታ ብረት ኢንዱስትሪ የተጣመሩት ግምረቻ ድርጅቶች ፡ ስቱትጋርት 1904(ገጽ 256,278-79)

5 ኸርግን ሌቪ ፡ ሞኖፖሊ ፡ ካርቴልና ትረስቶች ጀና1 909 ገጽ 286,290,298

6 ቲ. ኤች. ቮገልስቲን ፡ የካፒታሊስት ኢንዱስትሪ ፊናን ሣዊ ድርጅትና የሞኖፖሊዎች አመሠራረት ፡ የሶሺያል ኢኮ ኖሚክስ ግጠቃለያ የሞኖሲዎች አመሠራረት ፡ የሶሺያል ኢኮኖሚክስ ግጠቃለያ አቦትቱቢኘን 1914 ሲ. ኤፍ. በዚሁ ደራሲ የእንግላንድና የአሜሪካ የብረትና የከር ኢንዱስትሪ ድርጅታዊ ቅርጽ ፡ 1ኛ መጽሐፍ ሌይፐዚግ 1910

7 ዶክተር ሪየዘር ፡ በጀርመን ፡ የጀርመን ትልልቅ ባንኮችና ከጠቅላላ የኤኮኖሚ ዕድገት ጋር የተያያዘ ክምችታቸው ። 4ኛ ዕትም 1912፤ 7.149 ርበርት ሊየፍግን ፡ ካርቴሎችና ትረስቶች እና ምጣኔ ሀብታዊ ድርጅት የበለጠ መስፋፋት ፡ 2ኛ እትም 1910 ገጽ 25

12 ቲ. ኤች ቦገልስቴን የድርጅት ቅርጾች ገጽ 275

13 በትምባሆ ኢንዱስትሪ ኮርፖሬሽን ኮሚሽነር የቀረበ ዘገባ ዋሽንግተን 1909 ገጽ 266. ዶክተር ፖውሎስ ታፈል እንዳ ቀረበው ፡ የሰሜን አሜሪካ ትረስቶችና በቴክኒካዊ እር ምጃ ላይ ያላቸው ተጽዕኖ ስትትጋርት 1913 ገጽ 48

14 ዶክተር ፒ. ታፈል በዚሁ መጽሐፉ ገጽ 49

15 ሬይዘር ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ 3ኛ እትም ገጽ 547 ... ከጋዜጣው (ሰኔ 1916) የጀርመንን ኬሚካል ኢንዱስትሪ ስለሚያገናኘው አዲሱ ግዙፍ ትረስት አመ ሠራረት ዘገባ ያቀርባል ።

16 ኬስነር ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገ. 254

17 ኤሽዊግ ፡ « ሲሚንቶ » ዳይ ባንክ 1909 ቅጽ 1. ገ. 115

18 አ. ጀይደልስ ፣ የጀርመን ትልልቅ ባንኮች ከኢንዱስትሪ ጋር ያላቸው ግንኙነት ፣ ስለ ብረት ኢንዱስትሪ ልዩ ጥቅስ ሌይፐዚግ 1905 ገ. 271

19 አር. ሊየፍማን አክሲዮኖችና የፊናንስ ኩባንያ ገጽ.434.

20 ከዚህ በላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 465—66

21 ጀይድልስ ፣ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሔፍ ገጽ 108

22 አልፋሬድ ላንስበርግ ፣ የአምስት ዓመት የጀርመን ባንክ ሥራ ዳይ ባንክ ውስጥ 1913 ቁ. 8,ገጽ 728

23 ሹልዝ — ጋቬርኒትዝ ፣ የጀርመን የብድር ባንክ የሶሺያል ኤኮኖሚ ማጠቃለያ ቱቢናን 1915 ገ. 12 እና 137

24 አር. ሊየፍማን ፣ አክሲዮኖችና የፊናንስ ኩባንያዎች ስለ ዘመናዊ ካፒታሊዝም
1ኛ እትም ጀና 1909 ገጽ 212

25 አልፍሬድ ላንስበርግ ፣ የመያዣ ሥርአት በጀርመን የባንክ ሥራ ፣ በዳይ ባንክ 1910 ፤ ገ. 500

26 ኢጊን ኮፍማን ፣ የፈረንሣይ የባንክ ሥራ ፣ ቱቢፐ 1911 ገጽ 356 እና 362

27 ጂን ሊስኩር ፣ ቁጠባ በፈረንሣይ ፣ ፓሪስ 1914 ገጽ 52

28 ኤ. ላንስበርግ ፣ ባለ 300 ሚሊዮን ባንክ ፣ በዳይ ባንክ 1914 ገጽ 426

29 ትሺየርስኪ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 128

30 የብሔራዊ የገንዘብ ኮሚሽን ስታቲስቲክስ ፣ በዳይ ባንክ የተጠቀሰ 1910 ፣ ገጽ 1200

31 ዳይ ባንክ 1913 ገጽ 811 ፣ 1022 ፣ 1914 ገጽ 713
ዳይ ባንክ 1914 ገጽ 316

33 ዶክተር ኦስካር ስቲሊች ፣ ገንዘብና የባንክ ሥራ በበርሊን 1907 ገጽ 169

34 ሹሊዝ — ጋቨርኒትዝ የጀርመን የብድር ባንክ በሶሽያል ኤኮኖሚክ ማጠቃለያ ቱቢን 1915 ፣ ገጽ 101

35 ሪየዘር ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ 4ኛ እትም ፣ ገጽ 629

36 ሹሊዝ — ጋቨርኒትዝ የጀርመን የብድር ባንክ በሶሺያል ኤኮኖሚክ ማጠቃለያ ቱቪፐ 1915 ፣ ገጽ 151

37 ዳይ ባንክ 1912 ፣ ገጽ 435

38 በሹሊዝ ጋቨርኒትዝ የተጠቀሰ ፣ ከዚህ በላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 155

39 ፎይደልስ ፡ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ፡ ሪሰር ፡ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ

40 ፎይደልስ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 157

41 በኢገን ከፍማን የተጻፈ ፡ ስለፈረንሣይ ባንኮች በዳይ ባንክ ፡ 1909 ፤ 2 ፤ ገጽ 851 እና ተከታታዩ

42 ዶክተር አስካር ስቲሊቭ ፡ ገንዘብና የባንክ ሥራ በበርሊን 1907 ፡ ገጽ 148

43 ፎይደልስ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 183—84

44 ፎይደልስ ከዚህ በላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 181

45 አር ሂልፈርዲንግ ፡ ገንዘባዊ ወረት ፡ የሩሲያ እትም ሞስኮ 1912 ፡ ገጽ 338—39

46 አር. ሊየፍማን ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 476

47 ሃንስ ጊዲዮን ሄይማን ፡ ከጀርመን ትልቅ የብረት ኢንዱስ ትሪ የተቀላቀለ ፋብሪካ ፡ ስቱትጋርት 1904 ገጽ 268—69

48 ሊየፍማን አክሲዮኖች ፡ ወዘተ . . . ገጽ 258 የመጀመሪያው ሪያው እትም

49 ሹልዝ ጋቨርኒትዝ ፡ የሶሺያል ኢኮኖሚክ ግጠቃለያ ቅጽ 2 ፤ ገጽ 110

50 ኤል. አሽዌግ ፡ ግልገል ኩባንያዎች ፡ በዳይ ባንክ ፡ 1914 ፡ ገጽ 545

51 ኩርት ሄይኒግ ፡ የኤሌክትሪክ ትረስት ፈለግ በአዲስ ዘመን (ዳዜት) 1912 ፡ 30 ጃሀርግ ፡ 2 ፡ ገጽ 484

52 ኤ. አግሀድ ፡ ትልልቅ ባንኮችና የአለም ገበያ ። የትልልቅ ባንኮች ኤኮኖሚያዊና ፖለቲካዊ ምንነት ፤ በሩሲያ ብሔ ራዊ ኤኮኖሚና ፡ የጀርመንንና የሩሲያን ዝምድና በመጥ ቀስ ፡ በርሊን 1914

53 ሊሲስ ፡ በፈረንሣይ ፡ በፈረንሣይ አሊጋርኪን በመቃወም 5ኛ እትም ፡ ፓሪስ 1908 ገጽ 11-12 26 ፤ 39 ፤ 40 ፤ 48 ፤

54 ዳይ ባንክ 1913 ቁጥር 7 ገጽ 630

55 ስቲሊቮ ፡ የጀርመን ብሔራዊ ኤኮኖሚ ፡ በአሥራ ዘጠነ ኛው ምዕተ ዓመት 2ኛ እትም 1909 ገጽ 529 ቁጥር 8

56 ገንዘባዊ ወረት ገጽ 172

57 ስቲሊቮ ፡ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 138 ፡ ሊየፍማን ገጽ 51

58 በዳይ ባንክ፥ 1913 ገጽ 952 ኤል ኤሾዊና ፣ ያ ፣ ማተ ፣ ከዚህ በላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ውስጥ 1912 ፣ ቁ. 1 ገጽ 223 እና ተከታዩ

59 ርሸኬርስተርስ በዳይ ባንክ 1914 ቁጥር ፣ ገጽ 89

60 የባንክ ማኅኀት ፣ በዳይ ባንክ 1909 ፣ ቁጥር 1 ገጽ 79

61 በዚሁ መጽሐፍ ውስጥ ፣ ገጽ 301

62 በዚሁ መጽሐፍ ውስጥ 1911 ፣ 2 ገጽ 825 ፣ 1913 ፣ 2 ፣ ገጽ 962

63 ኢ. አግሀድ ፣ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 202

64 የኢንተርናሽናል ስታቲስቲካል ኢንስቲቲዩት ቡለቲን ፣ ገጽ 19 2ኛ መጽሐፍ 1912

ትንንሽ መንግሥታትን በሚመለከት የተሰጠው የሁለተኛ ኮለምን ዳታ በ1902 አሀዞች ላይ 20 እጅ በመቶ እየታከለ በግምት ነው የተወሰደው ።

65 ሆብሰን ፣ ኢምፔሪያሊዝም ፣ ሎንዶን ፣ በ1902 ገጽ 58 ሪየ ዘር፣ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 395 እና 404 ፒ. አርዶት ፣ የዓለም ምጣኔ ሀብት መዛግብት 7ኛ መጽሐፍ 1916 ገጽ 35

ሄይማርክ ፣ በቡለቲን ሂልፈርዲንግ ፣ ገንዘባዊ ወረት ገጽ 492 ሌይድ ጆርጅ ፣ በሀውስ ኦፍ ኮሜንስ የተደረገ ንግግር ግን ቦት 4 1915 በዴይሊ ቴሌግራፍ ግንቦት 5 1915 የቀረበ ፣ ቢ. ሀርምስ ፣ የአለም ኢኮኖሚ ችግር ፣ ጄና 1912 ገጽ 235 እና ተከታዩ . . ዶክተር ሲግመንድ ሺልደር ፣ የአለም ምጣኔ ሀብት ዕድገት ፣ መልክ በርሊን 1912 1ኛ መጽሐፍ ገጽ 150 ፣ ጆርጅ ፔይሽ ፣ «የታላቋ ብሪታኒያ የወረት አጠቃቀም ፣ ወዘ ተ . . . » የሮያል ስታቲስቲካል ኢንስቲቲውት ጋዜጣ ፣ 74ኛ መጽሐፍ 1910—11 ገጽ 167 ወዘተ . . ጆርጅ ዲዮ ሪብ የጀርመን ባንኮች በውጪ መስፋፋት ከጀርመን የም ጣኔ ሀብት ዕድገት ጋር ተያይዞ ፣ ፓሪስ 1909 ገጽ 84

66 ዳይ ባንክ 1913 2ኛ መጽሐፍ ገጽ 1024—

67 ሺልደር ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 346 ፣ 350 እና 371

68 ሪየዘር ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ 4ኛ እትምት ፣ ገጽ 375 ዲዮሪሽ ፣ ገጽ 283

69 የአሜሪካ የፖለቲካዊና የኅብረተሰብ ሣይንስ አካዳሚ ታሪክ 59ኛ ቅጽ ግንቦት 1915 ገጽ 301 በዚሁ ቅጽ ውስጥ በገጽ 331 የታወቀው ስታቲስቲሽያን ፔይሾ ፣ ዘ ፣ ስታቲስት በሚ

ለው የፊናንስ መጽሔት ውስጥ ኢንግላንድ ፣ ጀርመን ፣ ፈረንሳይ ፤ ቤልጅየምና ሆላንድ ወደ ውጪ የላኩት ካፒታል 40,000,000,000 ማለት 200, 000,000,000 ፍራንክ ይሆናል ብሎ ገምቷል ።

70 ጂይደልስ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 232

71 ሪየዘር ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ፤ዲዮሪሽ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 239
ኩርት ሄይኒንግ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ

72 ጂይደልስ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 193

73 ዲዮሪሽ ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 245—

74 ዳይ ባንክ 1912 ፣ 2 ፣ ገጽ 629 1036 ፣ 1 ፣ 388

75 ሪየዘር ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 125

76 ቮግልስቴይን ፣ የድርጅት ቅርጽ ገጽ 100

77 ሊየፍማን ካቴልና ትረስት 2ኛ እትም ገጽ 161

78 ኤ. ሱፓን የአውሮፓውያን ቅኝ ግዛት ማስፋፋት 1906 ገጽ 254

79 ሄንሪ ሲ. ሞሪስ ፣ የቅኝ ግዛት ታሪክ ፣ ኒው ዮርክ 1900 ቅጽ 2 ገጽ 88 ቅጽ 1 ገጽ 419 ቅጽ 2 ገጽ 304

80 አዲስ ዘመን (ኖይ ዳዜት) 16 ፣ 1 ፣ 1898 ገጽ 302

81 አዲስ ዘመን (ኖይ ዳዜት) 16 ፣ 1 ፣ 1898 ገጽ 304

82 ሲ. ፒ ሉካስ ፣ ታላቋ ሮማና ታላቋ ብሪታንያ ፣ ኦክስፎርድ 1912 ወይንም የዘ. አርል. ኦፍ ክሮመርስ ፣ ጥንታዊና ዘመናዊ ኢምፔሪያሊዝም ፣ ለንደን 1910

83 ሺልደር ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 38—42

84 ዋል ፣ ፈረንሣይ በቅኝ ግዛቶች ውስጥ በሄንሪ ሩዙዩ የተጠቀሰ ፣ የቪየና ቅርምት ፣ ፓሪስ 1905 ገጽ 165

85 ሹልዝ ጋቨርኒትዝ ፣ የእንግሊዝ ኢምፔሪያሊዝምና የእንግሊዝ ነጻ ንግድ በሃያኛው ምዕተ አመት መግቢያ ፣ ሌይፕዚግ 1906፣ ገጽ 318 ሣርቶ ሪየስቪ . ዋልተርሽዘንም ፣ ካፒታልን በውጭ ሥራ ላይ በማዋል የብሔራዊ ኤኮኖሚ ሥርአት ፣ በሚለው ጽሑፍ እንደዚሁ ነው የሚለው በርሊን 1907 ፣ ገጽ 46

86 ሺልደር ከዚህ ቀደም የተጠቀሰው መጽሐፍ ቅጽ 1 ፣ገጽ 160—61 ፤

87 ጂ. ኤ ድሮውልት ፣ ኅብረተሰብአዊና ፖለቲካዊ ችግሮች ፓሪስ 1900 ገጽ 299

88 አዲስ ዘመን1914 ቅጽ ፣ 2 እና 3 መጽሐፍ ገጽ 909 መስከረም 11 1914 ለማወዳደር 1915 ፣ 2. ገጽ 107 እና ተከታዩ

89 ሆብሰን ፤ ኢምፔሪያሊዝም ፣ ለንደን ፣ 1902 ገጽ 324

90 አዲስ ዘመን ፣ 1914 ፣ ቅጽ 2 እና 32ኛ መጽሐፍ ገጽ 921 መስከረም 11 ሲነጻጸር 1915 ገጽ 107 ወዘተ . . .

91 አዲስ ዘመን 1915 ፣ 1 ፣ ገጽ 144 ሚያዝያ 30 ፣ 1915

92 አር. ካልወር ፣ የአለም ምጣኔ ሀብት መግቢያ ፣ በርሊን 1906

93 በቅንፍ ውስጥ ያሉት አሀዞች ፣ በቅኝ ግዛት ውስጥ ያለውን የሕዝብ ብዛትና የግዛት ስፋት ያሣያሉ

94 ለጀርመን .. የስታቲስቲክስ አመታዊ መጽሐፍ 1915 የባቡር መዛግብት 1892 ፣ በተለያዩ አገሮች ተይዘው ለነበሩት ቅኝ ግዛቶች የሚደረገው የ1890 የባቡር መስመር ዕደላ ጥቃቅኖቹ ነገሮች በዓመት የተወሰዱ ናቸው ፤

95 ለማወዳደር ፣ ኤድጋር ክራሞንድ ፣ የእንግሊዝና የጀርመን አዪዎች የኤኮኖሚ ግንኙነቶች ፣ በሮያል የስታቲስቲክ ሶሳይቲ ጆርናል ፣ ሐምሌ 1914 ገጽ 377 እና ተከታዩ

96 ሆብሰን ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 59፤ 60

97 ሹልዝ ጋቨርኒትዝ ፣ የእንግሊዝ ኢምፔሪያሊዝም ገጽ 320 እና ተከታዩ

98 ሳርቶሪየስ ቮን ዋልተርሾዝን ፣ ብሔራዊው ኤኮኖሚያዊ ሥርአት ፣ ወዘተ . . . በርሊን 1907 ቅጽ 4

99 ሺልደር ፣ ከዚህ ቀደም የተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 393

100 ሹልዝ ፣ ጋቨርኒትዝ ከዚህ ቀደም የተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 122

101 ዳይ ባንክ ፣ 1911 1ኛ መጽሐፍ ፣ ገጽ 10 እስከ 11

102 ሆብሰን ፣ ከዚህ ቀደም የተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 103,205 144,335—386

103 ጌርሀርድ ሂልደብራንድ ፣ የኢንዱስትሪያሊዝምና የኢንዱስትሪያዊ ህብረተሰብአዊት አገዛዝ መንኮታኮት ፣ 1910 ገጽ 229 እና ተከታዩ

104 ሹልዝ — ጋቨርኒትዝ ፣ የእንግሊዝ ኢምፔሪያሊዝም ገጽ 301

105 የጀርመን አጼ ስታቲስቲክስ ቅጽ 211

106 ሄንገር የፈረንሣይ የገንዘብ አጠቃቀም ፣ ስተትጋርት ፣ 1913

107 ሁርዊች ፣ ስደትና ወዝ ኒውዮርክ 1913

108 የማርክስና ኤንግልስ የደብዳቤ ልውውጥ ቅጽ 2 ገጽ 290 ቅጽ 4 ገጽ 453 — ካርል ኮትስኪ ፣ ሕብረተሰብ አዊነትና የቅኝ ግዛት ፖለቲካ ፣ በርሊን 1907 ገጽ 79 ፤ ይህ መጽሔት ኮትስኪ ድሮ ገና ማርክሲስት በነበረበት ጊዜ የተጻፈ ነው ።

109 የሩሲያ ሶሺያል ትምክህተኝነት ፣ ባን ፖትሮሶቫች ፣ ሴኬን ኬሊሶች ማገዘሎቨት ወዘተ . . . . . ይፋ በወጣበት ቅርጹ እንዲሁም በነ ሸከሄድዝ ስኮብሌቭ ፣ አክስለርድ፤ ማርቶቭ ወዘተ . . . . በሥውር ቅርጹ ፣ በተጨማሪም ከተለ ለያየ የሩሲያ አድርባይነት ፣ እሱም ሊኩዴሽኒዝም (ደም ሳሽነት) ብቅ አለ ።

110 የአለም ኤኮኖሚ መዛባት ቅጽ 2 ገጽ 193

111 ፓቱዮሌት ፣ የአሜሪካ ኢምፔሪያሊዝም፡ዲጆን 1904 ገጽ 272

112 የኢንተርናሽናል ስታቲስቲክስ ኢንስቲትዩት ቡለቲን 19ኛ 2ኛ መጽሐፍ ገጽ 225

113 136 ኮትስኪ ፣ ብሔራዊ መንግሥት ፣ ኢምፔሪያሊስት መንግሥትና የመንግሥታት አንድነት ፣ ኑርበርግ 1915 ገጽ 72 እና 70

114 ገንዘባዊ ወረት ገጽ 567

115 ዳይ ባንክ 1909 ቅጽ 2 ገጽ 819 እና ተከታዩ

116 አዲስ ዘመን ሚያዝያ 30 1915 ፣ ገጽ 144

117 ዴቪድ ጃይን ሂል ፣ በአውሮፓ የአለም አቀፍ እድገት የዲፕሎማሲ ታሪክ ቅጽ 1 ገጽ 10

118 ሺልደር ከዚህ ቀደም በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 178

119 ገንዘባዊ ወረት ገጽ 487

120 የሶሺያል ምጣኔ ሀብት መሠረተ ሃሣቦች ገጽ 146

ማ ስ ታ ወ ሻ

ኢምፔሪያሊዝም ፣ ከፍተኛው የካፒታሊዝም የዕድገት ደረጃ በ1916 ዓ.ም. የመጀመሪያው አጋማሽ ላይ ነበር የተጻፈው። በ1915 ዓ ም ሌኒን በርን በነበረበት ጊዜ ፣ በብዙ ሀገሮች

ውስጥ ታትመው የነበሩ አያሌ ጽሑፎችን ግጥናት ጀመረ። መጽሐፉን ፥ በጥር ወር 1916 ዓ ም መጻፍ ጀምሮ ፥ በወሩ መጨረሻ ላይ ወደ ዙሪክ ሄደ። ጽሑፉን በዙሪክ ካንቶን ቤተ መጻሕፍት ቀጠለ ። ከ40 የማተሚያ ገጾች በላይ የወጣቸውን አያሌ የተጨመቁ የውጪ የመጽሐፍ ክፍሎችን ፥ ማጠቃለያዎችን ፥ ማስታወሻዎችንና መዘርዝሮችን ፥ ከመቶ በላይ ከሚሆኑ በተለያዩ ቋንቋዎች ከተጻፉ መጽሐፍት፤መጽሔቶች፣ ጋዜጦችና፥ ስታቲስቲካዊ ፍሬ ነገሮች አጠናቅረ ። እነ ዚህ ጽሑፎች ፥ በ1939 ዓ. ም. ስለ ኢምፔሪያሊዝም ማስ ታወሻ ደብተሮች በሚል ርዕስ በተለያዩ የድርሰት መልክ ታትመው ነበር ።

ሰኔ 19 ሐምሌ2 1916 ዓ ም ስለ ኢምፔሪያሊዝም የጻፈውን ያለቀለት የእጅ ጽሑፉን ፥ ሌኒን ለፓሪስ አታሚዎች ላከ ። በግኔጅሜንት መሐል ያሉ የሚንሼቪክ አባላት ፥ በኮትስኪ ና በሩሲያ ሜንሼቪኮች (ማርቶቭና ኩባንያው) አድርባይ ንድፈ ሀሣብ ላይ የከረረ ሂስ የያዘውን የመጽሐፉን ክፍል ሠርዘው አውጥውት ነበር ፥ ፕሬራስታኒዩ (ካፒታሊዝም ወደ ካፒታሊስት ኢምፔሪያሊዝም ሲያድግ የሚለውን የሌ ኒን አባባል ፥ ወደ ፕሬቭራሽቴንየ (መለወጥ ) ተቀይሯል ፥ ሪአክሲዮን ካራክተር( የከፍተኛ ኢምፔሪያሊዝም ንድፈ ሃሳብ ጸረ ተራማጅ አቋም) ወደ አትስታሊ ከራክተር (ወደኋላ ቀር ጠባይ) ተለውጧል፤ወዘተ በ1917 ዓ. ም. መጽሐፉ ኢምፔሪ ያሊዝም የካፒታሊዝም የመጨረሻ የዕድገት ደረጃ ፥ በሚል ርዕስ ፥ በፓሪስ አታሚዎች ፥ ታትሞ ወጣ ። ወደ ሩሲያ ከተ መለሰ በኋላ ፥ ሌኒን ፥ በመስከረም ወር 1917 ዓ. ም. የቀን ብርሃን ላየው መጽሐፍ መግቢያ ጻፈለት ።

ኢምፔሪያሊዝም የካፒታሊዝም ከፍተኛ የዕድገት ደረጃ ስለሚለው መጽሐፍ ጠቃሚነት ለመረዳት ፥ የሶቪየት ዩን የን(ቦልሼቪኮች) ኮሚዩኒስት ፓርቲ ታሪክ ይመልከቱ ። አጭር ትምህርት የእንግሊዝኛ እትም ሞስኮ 1950 ገጽ 207 እስከ 79

የዚህን መጽሐፍ ገጽ 146—48 ይመልከቱ

ይህ መግቢያ ለመጀመሪያ ጊዜ የታተመው« ኢምፔሪያሊ ዝምና ካፒታሊዝም » በሚል ርዕስ ሥር በኮሚዩኒስት ኢን ንተርናሽናል ቁ. 18 ጥቅምት 1921 ገጽ 3 ነበር ።

በዚህ እትም ማኔፌስቶው ታትቷል ።

አንድ ሴንትሪስትፓርቲ በሚያዝያ 1917 ተመስርቶ ነበር። የዚህ ፓርቲ አባላት የወዝ የጋራ ብልጽግና ኮትስካይቶች ነበሩ ። ከነፃ የኅብረተሰብ ትምክህተኞች ጋር አንድነትን ለፈፉ ፣ ረዷቸውና ተከላከሉላቸው ፣ እና የመደብ ትግሉን ለመተው ጠየቁ

በጥቅምት ወር 1920 ዓ. ም. በአይ ኤስ ዴ. ፒ. ጂ. ኮንግሬስ ላይ ፣ ሀለ ውስጥ ለሁለት ተከፈሉ ። በታኅሣሥ ወር ከፓር ቲው አባላት ይበልጡ ከጀርመን ኮሚኒስት ፓርቲ ጋር ተዋ ሃዱ ። የቀኝ ክንፍ አባላት የተለየ ፓርቲ በማቋቋም የቀድ ሞውንና እስከ 1922 ዓ. ም. ዕድሜ የነበረውን አይ. ኤስ. ዴ. ፒ. ጅ. የሚለውን ስም ወሰዱ ።

ስፓርታሲስቶቹ ፣ በካርል ሊምንሸት ፣ ሮዛ ሉክሰንበርግ ፣ ፍራንዝ ሜህረንግ፣ክላራ ዜትኪንና በሌሎችም መሪነት ፣ በአ ንደኛው የዓለም ጦርነት መግቢያ ላይ የተቋቋመው ፣ የጀር መን ግራ ክንፍ ሶሺያል ዲሞክራቲክ አብዮታዊ ድርጅት የስፓርታክስ ሊግ አባል ነው ። የኢንተርናሽናል ቡድን በመባልም ይታወቅ ነበር። ስፓርታሲስቶች፣ የኢምፔሪያሊ ሊስቱን ጦርነት በመቃወም ፣ ሕዝቡ መሐል አብዮታዊ ፕሮፓጋንዳ ያካሄዱ ነበር ፣ የጀርመንን ኢምፔሪያሊዝም የዘረፉ ፖሊስና የአድርባይዮቹን የሶሺያል — ዲሞክራቲክ መሪዎች መክዳት አጋለጡ ። ይሁን እንጂ ስፓርታሲስቶቹ፣ እራሳቸውን ፣ የንድፈ ሃሳብንና ፖሊሲን በሚመለከቱ አንገብጋቢ ጥያቄዎች ላይ ለይቶ፣ማጽዳት አቃታቸው። ከሬል ሜንሼቪክ የሆነ የኢምፔሪያሊዝምን ንድፈ ሃሳብ አስተጋቡ ። የብሔሮችን የራስን በራስ መወሰን የማርክሲስት አተረጓ ጎም ሳይቀበሉ ቀሩ (ማለትም እስከ መገንጠል ድረስና ተገን ጥሎም የራስን መንግሥት ማቋቋም)በኢምፔሪያሊዝም ወቅት ብሔራዊ ነጻ አውጪ ጦርነቶች ሊካሄዱ መቻላቸውን ካዱ ፣ ለአብዮታዊው ፓርቲ ዝቅተኛ ግምት በመስጠት ለሠራተኛው መደብ ንቅናቄ ግብታዊነት አጐበደዱ።(የሶቪየት ዩኒየን (ቦል ሼቢቢኮች) ኰሚዩኒስት ፓርቲን ታሪክ ይመልከቱ ። አጭር ትምህርት የእንግሊዝ እትም ሞስኮ 1950 ዓ. ም. ገጽ 42—45) ። የጀርመን ግራዎች ስላደረጓቸው ስህተቶች ትችት ፡ « ዘ ጁኒየስ ፓምፍሌት» (ስብስብ ሥራዎች 4ኛ የሩሲያ እት ም 22ኛ መጽሐፍ ገጽ 291—305)«ኤ ካሪኬቸር ኦፍ ማርክ ሲዝም እና አምፔሪያሊስት ኤኮኖሚዝም» በተባሉት የሌ ኒን ጽሑፎች ውስጥ ተሰጥቷል ። «የቦልሼቪዝምን ታሪክ በማመልከት ጥቂት ጥያቄዎች»(ሥራዎችእትም ሞስኮ1955 13ኛመጽ. ገጽ 86 እስከ104) ። በ1917 ዓ. ም. ስፓርታሲ

ስቶቹ ከጀርመን ሴንትሪስት ነፃ ሶሺያል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ተደባለቁ ፤ ነገር ግን ከድርጅታዊ አንጻር ብቻቸውንቀሩ ። ኳኅዳር 1918 ዓ ም የጀርመን አብዮት በኋላ ከፓርቲው ተገነጠሉ ፤ እና በዚያው ዓመት በታኅሣሥ ወር የጀርመንን ኮሚዩኒስት ፓርቲ መሠረቱ ።

7. በዚህ እትም የደራሲው የጥቅስ ምንጮችና ማስታወሻዎች ነገርጌ ማርታወሻ ውስጥ ተመልከተዋል ።

8. ካርል ማርክስ ፣ ካፒታል ጀርመን እትም በርሊን 1919 3ኛ መጽሐፍ 655

9. በአሥራ ዘጠነኛው ምዕተ ዓመት ፣ በሰባዎቹ ዓመት ምሀረቶች መጀመሪያ ላይ ፣ በመጥፎ ዓላማ በመነሳሳት ርስትና መተማመኛዎችን በመግዛትና ሲወደዱ መልሶ በመሸጥ ፣ በርካታ ገንዘብ ሲያገኙ በነበሩ ነጋዴዎች የተገዙ ፣ የጆይንት ስቶክ ኩባንያዎች መመሥረት በተስፋፋበት ጊዜ የተፈጸመ ሁኔታ ነው ።

10. ፍራንክፈርተር ዜይቱንግ የፍራንክፈርት ጋዜጣ) ከ1856 ዓ ም እስከ 1945 ዓ. ም. በጀርመን ንዑስ ከበርቴ ዲሞክራቶች ፣ ፍራንክፈርት በ ሜይን ውስጥ በየዕለቱ እየታተመ ይወጣ የነበረ ጋዜጣ ።

11. ሌኒን ጂ. ቢ. ፕሌካኖቭ ማለቱ ነው

12. ፕሮድጐል በ1906 ዓ. ም. የተመሠረተው የካደኔትስ ሸለቆ የሚያወጣውን የነዳጅ ማዕድን ለሚነግድ የሩሲያ ኅብረተሰብ የተሰጠ ማኅጸረ ቃል ። ፕሮዳሜት—በ1901 ዓ ም የተመሠረተው ፣ የሩሲያን ከብረታ ብረት የተሠሩ ዕቃዎች የሚሸጥ ኅብረተሰብ ።

13. በፈረንሣይ ፣ በ1892-93 የነበረው ከሚታመነው በላይ የባለሥልጣኖች በሥልጣን ያለአግባብ መጠቀምና ጉቦ ፣ የፈረንሳይ ፓናማ ካናል ኩባንያ ጉቦ የሰጣቸው ባለሥልጣኖች በጋዜጦች መጋለጥ ።

14. በዚህ መጽሐፍ ገጽ 93—94 ይመልከቱ

15. ካርል ማርክስና ፍሬድሪክ ኤንግልስ ምርጥ የደብዳቤ ልውውጥ የጀር. እትም በርሊን 1953 ገጽ 131—32

16. ካርል ማርክስና ፍሬድሪክ ኤንግልስ ምርጥ የደብዳቤልውውጥ የጀር እትም በርሊን 1950 ገጽ 608 — 09

17. ሜንሼቪኮች ኤም አይ ናኪምሰን

18. ካርል ማርክስ ካፒታል ጀር እትም በርሊን 1959 3ኛ መጽ ገጽ 142

